

# የቦሌ ክፍለ ከተማ የወረዳ 01 ብልጽግና ፓርቲ ጽ/ቤት አደረጃጀት ዘርፍ የ2017 ዓ.ም መነሻ እቅድ

**ሐምሌ 2016 ዓ.ም**

## 1.መግቢያ

በ2016 ባለፈው በጀት ዓመት በሰራናቸው ስራዎች ብልፅግና ፓርቲ በሀገራችን ኢኮኖሚያዊ፣ፖለቲካዊ፣ማህበራዊና ዲፕሎማሲያዊ ዘርፎች ተጨባጭ ውጤቶችን ያስመዘገበባት ዓመት ነዉ፡፡ በአንድ በኩል ከለውጡ ወዲህ በተሠሩ ሥራዎችና በተመዘገበው ውጤት ከፍተኛ ተስፋ በህዝብ ዘንድ የተፈጠረበት በሌላ መልኩ ደግሞ በውስጣዊና ውጫዊ ምክያቶች በተፈጠረው የኑሮ ውድነት እንዲሁም በኢትዮጵያ ጠላቶች በሚደረገው የሰላም ማደፍረስ እኩይ ተግባር በሚፈጠረው የሰላም መታወክ ምክንያት ብልፅግና ፓርቲና መንግስት እነዚህን ችግሮች በመፍታት ፓርቲው ለህዝብ የገባውን ቃል በተግባር ያሣየበት በተጨባጭ የሚታዩ ውጤቶች የተገኘበት ዓመት ነበር፡፡

ከዚህም ባለፈ በኅብረተሰባችን ውስጥ የሚታየው የዕድገት ፍላጎት በዓይነትም በመጠንም በከፍተኛ ደረጃ እያደገ ከመሆኑም ባሻገር የተለዋዋጭነት ምጣኔው በጣም ፈጣን መሆኑ ብዙ ሥራ የሚፈልጉ እንደሆነ መገንዘብ ይቻላል፡፡ፓርቲያችን በዚህ ሁኔታ ውስጥ ሆኖ ሀገራችን እና  ህዝቦችዋን በመምራት ላይ የሚገኝ ስለሆነ ከመቼውም ጊዜ የበለጠ ጠንካራ አመራር የመስጠት ታሪካዊ ሃላፊነት  ያለበት መሆኑን መገንዘብ ይኖርብናል፡፡ ፓርቲው በየደረጃው የሚገኘው ዓመራር በማጠናከር የፓርቲው ቀይ መስመር ተብለው የተለዩት ሌብነትና ፅንፈኝነትን ደረጃ በደረጃ በማክሰም ውጤታማ ስራዎችን ማከናወን የሚያስችሉ ስራዎች ላይ ትኩረት ሰጥተን ማከናወን  የሚጠበቅብን ይሆናል፡፡
በመሆኑም ብልፅግና ፓርቲ እስካሁን ያስመዘገባቸውን ስኬቶች ጠብቆና አጠናክሮ ለመዝለቅ እንዲሁም ችግሮችን በተባበረ ክንድ በመሻገር በምርጫ ወቅት ቃል የተገቡ ጉዳዮች እና የጉባኤዉ ዉሳኔዎችና አቅጣጫዎችን በየደረጃው ያሉ የፓርቲ አደረጃጀቶችን በመጠቀም በቁርጠኛ የአመራርና የአባላት ትግል እና በህዝብ ተሳትፎ ያረጋገጠ እቅድ በማዘጋጀት የነቃ ተሳትፎ በሚያረጋግጥ መልኩ መፈጸም የግድ የሚሆንበት ግዜ ላይ እንገኛለን፡፡

ስለሆነም እነዚህ ከላይ ያስቀመጥናቸው አበይት ኩነቶች ከመደበኛ የፓርቲ ስራዎቻችን ጋር በማስተሳሰር ለመፈጸም ከምንግዜውም የበለጠ ለህዝብ የገባነው ቃል በከፍተኛ ቁርጠንነትና ዲሲፕሊን በግዜ የለንም መንፈስ መረባረብ የግድ የሚለን ይሆናል፡፡ በመሆኑም የ2017 ዓ.ም ዕቅድ ሶስት ዋና ዋና ክፍሎች ይዞ እንዲዘጋጅ ተደርጓል፡፡ የመጀመሪያው ክፍል የመነሻ ሁኔታ ትንተና፣ ሁለተኛው ክፍል ዓላማ፣ ግቦችና ዝርዝር ተግባራት፣በሦስተኛው ክፍል የአፈጻጸም

አቅጣጫዎችና ስልቶች፤ ክትትልና ድጋፍ እንዲሁም ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮችና መፍትሄዎችን እና የግዜ ማዕቀፍ በማካተት እንዲዘጋጅ ተድርጓል፡፡

## 1. ክፍል አንድ፡- የዕቅዱ መነሻ ሁኔታዎች ትንተና

### 2.1 መነሻ ሁኔታዎች

#### 2.1.1 ዓለማዊ እና ቀጠናዊ ሁኔታ እንደመነሻ

ኢትዮጵያ እንደ አንድ አለም አቀፍ የፖለቲካና የኢኮኖሚ ተዋናይ ሀገር በአለም አቀፍና ቀጣናዊ ጉዳዮች በሚኖራት ድርሻ እንዲሁም ባላት ስትራቴጂካዊ አቀማመጥ፣ ታሪካዊ ዳራና ነባራዊ ሁኔታ፣ በተለይም ደግሞ ከሀገራዊ ለውጡ ወዲህ እያበረከተች ባለችው ፖለቲካዊና ዲፕሎማሲያዊ አስተዋፆ የተነሳ በበጎም ይሁን በክፉ አለማዊና ቀጠናዊ ሁኔታዎች ተፅዕኖ ያሳድሩባታል፡፡ በተመሳሳይ ሁኔታ ከተማችን አዲስ አበባም በሀገር ደረጃ ባላት ድርሻ ብቻ ሳይሆን በአለም አቀፍ የዲፕሎማሲ መናሃሪያነቷና የበርካታ አለምአቀፋዊ፣ አህጉራዊና ቀጠናዊ ተቋማት መቀመጫነቷ የሚያሳርፍባት ጫና ቀላል ግምት የሚሰጠው አይደለም፡፡ በመሆኑም በ2016 በጀት አመት የፓርቲ ስራዎች እቅድ ላይ በዚህ ዓለማዊ እና ቀጠናዊ ሁኔታ ውስጥ ከከተማችን አንፃር ቀጥተኛ ትስስር ባላቸው ጉዳዮች ላይ ማተኮር እንደ አንድ መነሻ መውሰዱ ተገቢ ይሆናል፡፡

የሩሲያና የዩክሬይንን ጦርነት መነሻ አድርጎ በኃያላኑ ሀገራት መካከል የተከሰተው ግጭት የዓለምን የኢኮኖሚ ሥርዓት በማናጋት በምግብ እና በነዳጅ  ምርቶች ላይ ከፍተኛ የዋጋ ጭማሪ በማስከተል የምግብ ምርቶችና የሸቀጦች አቅርቦት እጥረት እንዲከሰት ምክንያት ሆኗል፡፡ ይህ ዓለም አቀፍ ክስተት በሀገራችን ብሎም በከተማችን ለተከሰተው የምርት እጥረትና የዋጋ ንረት አይነተኛ መንስዔ ሆኖ ቆይቷል፤ በዚህ አመትም እንደሚቀጥል ይጠበቃል፡፡ በከተማችን የተከሰተዉን መሰረታዊ የፍጆታ ምርቶች ዕጥረት ለመቅረፍና ጫናዉን ለመቋቋም የተለያዩ የገበያ ማረጋጊያ እርምጃዎች በመወሰዳችውና በበጎ አድራጎት ስራዎች የተነሳ ክስተቱ በከተማችን ባለው አነስተኛ ገቢ ነዋሪ ላይ ሊያደርስ ይችል የነበረውን እጅግ የከፋ ችግር መቋቋም ተችሏል፡፡ አሁን ደግሞ በጦርነቱ ቀጥተኛ ተሳታፊ የሆኑት ሃያላን ሀገራት በድርድርና በተናጠል በሚወስዷቸው ርምጃዎች የተነሳ እንደ ነዳጅ እና የምግብ ዘይት ባሉ ምርቶች ላይ የአቅርቦትና የዋጋ መረጋጋት እየታየ ሲሆን የዘይት ዋጋ በተለይ ደግሞ ቅናሽ

ማሳየት ጀምሯል። ይህንን አለማዊ ሁኔታ ለተግባቦት ስራና ለዘላቂ የዋጋ መረጋጋት አስተዋፆ በሚያመጣ ሁኔታ መጠቀም የምንችልበት እድሉ አለን።

በጎረቤታችን ሱዳን ያጋጠመው ግጭት በዛች ሀገር በሚኖሩ የሀገራችን ዜጎች ላይ ያስከተለው ጉዳት እንዳለ ሆኖ በክረምቱ ወራት ወደ ሀገራችንና ወደ አዲስ አበባ በሚገባው የሽንኩርት ምርት አቅርቦት ላይ መስተጓጎል በመፍጠሩ በከተማችን የሽንኩርት ዋጋ እንዲንር አድርጎታል። ይህ አካባቢያዊ ሁኔታ በሀገራቱ ባለቤትነትና በሌሎች ሀገራትና ተቋማት እልባት ሊሰጠው እንደሚችል ተስፋ ቢደረግም እኛ ግን ከጥገኝነት የሚያላቅቁን የመፍትሄ አማራጮች መስራት አለብን። አካባቢያዊ ሁኔታው በከተማችን የሚካሄደውን የከተማ ግብርና እንድናስፋፋ እንዲሁም ዘላቂ ሀገራዊ ምንጮች ላይ እንድናተኩር የሚገፋን ነው።

## 2.2 ሀገራዊ ሁኔታ እንደመነሻ

የፓርቲያችን አንደኛ ጉባዔ ባስቀመጠው አቅጣጫ መሰረት ሀገራችን ከስንዴ ለማኝነት የተላቀቀችበት ሁኔታ የተፈጠረ ሲሆን ወደ ውጪ ሀገራትም መላክ ጀምራለች። በአንፃሩ የከተማችን አብዛኛው ነዋሪ በስንዴ ምርት ላይ በከፍተኛ ደረጃ ጥገኛ በመሆኑና በአቅርቦትና ስርጭቱ ላይ ባሉ ሰው ሰራሽ ችግሮች የተነሳ በድጎማ ዳቦ ለሚያቀርቡ ፋብሪካዎች በቂ ግብዓት ማቅረብ አልቻልንም። ይህን እንደ መልካም አጋጣሚ የተጠቀመው ፅንፈኛ ሃይል አዲስ አበባን ማዕከል አድርጎ ሀገራችን በስንዴ ምርት እመርታ አምጥታ ሳይሆን ለአለም አቀፍ ፕሮፓጋንዳ ዘመቻ አድርጎ በማቅረብ ቀላል የማይባል ነዋሪያችንን በፈጠራ ወሬና መረጃ ሲመርዝ ይታያል።

ይህን የውሸት ፕሮጋንዳ ዘመቻ በመረጃ ላይ ተመስርቶ ማጋለጥ እንዳለ ሆኖ በአዲስ የፖለቲካ እይታ ተቃኝተን በከተማችን ነዋሪ የአመጋገብና የሀብት አጠቃቀም ላይ የባህል ሽግግር ለማረጋገጥ የሚያስችሉ እንቅስቃሴዎችን መጀመር ይኖርብናል። በከተማ ግብርና በምናመርታቸው እንዲሁም በስፋትና በተነፃፃሪ አነስተኛ ዋጋ ባላቸው የምግብ ምርቶች ላይ ያተኮረ ጤናማ የአመጋገብ ስልትን ማስተዋወቅ በንቅናቄና በጥናት ላይ በተመሰረተ የህዝብ ግንኙነት ስራ ልንፈፅመው የሚገባ ተልዕኮ ነው።

በሰሜኑ የሀገራችን ክፍል ከሁለት አመት በላይ የዘለቀው ጦርነት የሀገራችን የምንጊዜም ጠላቶች በውስጣችን ካሉ የጥፋት ሃይሎች ጋር በመቀናጀት ሀገራችንን ከቻሉ ለማፈራረስ፤ ካልሆነላቸውም ከያዘችው የብልፅግና ጉዞ ለማጨናገፍ እንዲንቀሳቀሱ ምቹ ሁኔታ ፈጥሮላቸው

እንደነበር ይታወቃል። መንግስታችን በወሰደው በሳል ውሳኔ ጦርነቱን በሰላም መቋጨት መቻሉ ተጨማሪ ጥፋቶች የታደገ ቢሆንም እነዚህ ሃይሎች አሁንም ያላቸውን እድል ሁሉ ተጠቅመው ሀገራችን እንዳትረጋጋና ተፈጥሯዊ ሀብቷን እንዳታለማ ከማገድ ወደ ኋላ አይሉም። ከዚህ አንፃር ኦነግ ሸኔንና ጽንፈኛ ፋኖን ጨምሮ በከተማችን ዙሪያና በውስጥ የሚንቀሳቀሱ የጥፋት ሃይሎችን ለመጠቀም መንቀሳቀሳቸው አይቀርም። በመሆኑም መላ የከተማችንን ነዋሪና የሰላም ሰራዊቱን በማነቃነቅ ውስጣዊ ሰላማችንን መጠበቅ እና በዚህም ሴራቸውን በማክሸፍ የከተማችንን የልማት ግስጋሴ ማስቀጠል ምንጊዜም የማንዘነጋው ተግባር መሆን ይኖርበታል።

የፓርቲያችንን የስራ አስፈፃሚ ኮሚቴ ውሳኔዎች ተከትሎ ለአመራራችንና አባላችን በተሰጠው ሀገር አቀፍ ስልጠና ላይ እንደታየው በከተማችን ለሚከሰቱ ችግሮች መንስዔው ክልሎች ብቻ እንደሆኑ አድርጎ የማየት አዝማሚያ በውስጣችን የታየ ሲሆን፤ በተቃራኒው ክልሎች ባደረጓቸው ውይይቶች ላይ ደግሞ የእነሱ ችግር ምንጭ አዲስ አበባ ነው ብሎ መደምደም ታይቶባቸዋል። ሀገራዊ ወቅታዊ ሁኔታችን ከዚህ አይነት እኛ እና እነሱ ከሚል ከፋፋይ አጀንዳ በፍጥነት ወጥተን ወደ ውስጣችን ማየትና ችግሮችን ከምንጫቸው ለማድረቅ የበኩልን ድርሻ መወጣትና በጋራ መረባረብ እንደሚያስፈልገን ያሳየናል።

### 2.3 የከተማችን ሁኔታ እንደመነሻ

አዲስ አበባ የኢትዮጵያ ሀገረ-መንግስት ዋና መቀመጫ ከመሆኗም በዘለለ ከታላላቅ የዓለማችን ከተሞች ተርታ የምትመደብ ከተማ ናት። አዲስ አበባ የአፍሪካ ህብረት መቀመጫና የዓለም የዲፕሎማሲ ተቋማት ማዕከል ብትሆንም ለበርካታ ዓመታት ከተከማቹ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ ችግሮች ሳትላቀቅ ቆይታለች። በመሆኑም ከተማችንን ያሉባትን ድርብርብ ሃላፊነቶች የሚመጥን ደረጃ ላይ ለማድረስ ካስፈለገ ፈጣንና ሁለንተናዊ እድገት ማስመዝገብ ግድ ይላል።

ፓርቲያችን ብልፅግና የከተማችን ዘርፈ ብዙ ችግሮች የሚፈቱበትን ስልት ቀይሶ ነዋሪዎቿን አሳታፊና ተጠቃሚ የሚያደርግ ሥርዓት መገንባት ጀምሯል። ከልማት፣ ከመልካም አስተዳደርና ከአገልግሎት አሰጣጥ ጋር የተያያዙ ውስብስብ ችግሮችን በመፍታት ከተማዋን ለነዋሪዎች ምቹ ለማድረግ የሚከናወኑ ተግባራት ዉጤታማ መሆን ጀምረዋል። የከተማዋን ገጽታ የቀየሩና ብልፅግናችን አይቀሬ መሆኑን ያሳዩ ትላልቅ ፕሮጀክቶች ተገንብተዋል።

አነስተኛና መካከለኛ ገቢ ያላቸዉን ነዋሪዎች ኑሮና ህይወት የሚቀይሩ ሰዉ ተኮር ሥራዎች አመርቂ ዉጤት ተመዝግቦባቸዋል። በ60 እና የ90 ቀናት ዕቅድ የተከናወኑ ተግባራት ሞዴል ወረዳዎችንና ክፍለ ከተሞችን መፍጠር ብቻ ሳይሆን በከተማችን ያሉ ማህበራዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ፖለቲካዊ ስብራቶችን በመጠገን፣ የባህል ሽግግር በማምጣትና ከአመራር እስከ ነዋሪ የስራ ባህልን በማሻሻል ውጤት የተገኙባቸው ናቸው።

እነዚህ ስኬቶች እንዳሉ ቢሆኑም ለከተማችን ነዋሪ ጉስቁልና ምክንያት የሆኑ ኢኮኖሚያዊ ችግሮች እና የኑሮ ጫናውን ያከበዱ የመልካም አስተዳደርና ብልሹ አሰራሮች አሉ። ስለሆነም በ2016 በጀት አመት መልካም አፈጻጸሞችን ወደ ሌሎች ክፍለ ከተሞችና ወረዳዎች ከማስፋት በተጨማሪ የሥራ ዕድል ፈጠራን ማጠናከር፣ የኢንቨስትመንት አማራጮችን ማስፋፋት፣ ጥራት ያለውን የኢኮኖሚ ዕድገት ማረጋገጥ፣ ምርታማነትና ተወዳዳሪነትን ማሻሻል፣ ፕሮጀክቶችን የመፈጸም አቅምን ማሳደግ፣ መንግስታዊ አገልግሎቶችን ማሻሻል፣ በሌብነት ላይ የተጀመረውን ትግል ማጠናከር፣ ከተማችንን ስማርት የማድረጉን ሂደት ማፋጠን፣ የግሉ ዘርፍ በኢኮኖሚው ውስጥ የሚኖረውን ሚና ማጎልበት እና እንደ መኖሪያ ቤትና ትራንስፖርት ያሉ አቅርቦቶችን ማሳደግ ይጠበቃል።

የከተማችንን ሰላም ከሚረብሹ ጉዳዮች አንዱ የብሔር ጽንፈኝነትና የሀይማኖት አክራሪነት ችግር ነዉ። ጽንፈኝነትና አክራሪነት በጽንፍ የፖለቲካ ኃይሎች፣ በሀይማኖት አክራሪዎች፣ በጽንፈኛ አክቲቪስቶችና ሚድያዎች ብቻ ሳይሆን በራሳችን አመራርና አባል ዉስጥም ብቅ ጥልቅ የሚል መሰረታዊ የፖለቲካ ስብራታችን መገለጫ ሆኗል። ስለሆነም በውስጣችን የሚስተዋለዉን ጽንፈኝነትና አክራሪነት ታግሎ መልክ በማስያዝ ህብረ ብሄራዊ አንድታችንን ማጠናከር በ2017 በጀት አመት ትኩረት የሚጠይቅ ጉዳይ ነው።

## 2.4 የመዋቅራችንና ሁኔታ እንደመነሻ

### 2.4.1 በየደረጃዉ ያለዉ የአመራራችን ሁኔታ

የከተማው የበላይ አመራር መደበኛ ተግባራትንና በየጊዜው የሚቀያየሩ ሀገራዊ ሁኔታዎችን ግምት ውስጥ በማስገባት የአመራር ስምሪት እያደረገ እንደሆነ ይታወቃል። የ90 ቀናት ዕቅድ ስራዎችን መሰረት በማድረግ ተግባራት በታቀደው አግባብ እንዲፈፀሙ ሊያደርግ የሚችል የስራ ክፍፍል በማድረግና ዋና ዋና ተግባራትን ተከፋፍሎ በመምራትና በማስተባበር ስራዎች

ተሳስረው እንዲፈፀሙ በሚያደርግ የተቀናጀ አመራር አሰጣጥ ውጤታማ ስራ እንዲሰራ አስችሏል። የበታች አመራሩን በተደጋጋሚ በፕላዝማ አማካኝነት ጭምር በቀጥታ በማግኘት በወቅታዊ አጀንዳዎች ላይ ግልፀኝነት መፍጠሩና ተልዕኮዎችን ማውረድ መቻሉ የሚበረታታ ተግባር ነው። ወቅታዊ ሁኔታን በማወቅና በመተንተን ይህን የሚመጥን የፖለቲካ ስራ በመስራት ጥንካሬዎችን የማስቀጠልና አሉታዊ ዝንባሌዎችን ደግሞ የማረም አቅጣጫ ተከትሎ እየተሰራ ይገኛል። በሌላ በኩል ችግሮች ተከስተው ሲገኙም እንደ ቀዉስ ግዜ አመራር ችግሮችን በማይባባሱበት አግባብ እንዳይስፋፉ የማድረግና ከዚህም ልምድ በመዉሰድ ዳግም እንዳይከሰቱ የሚያስችል ስራ ሰርቷል።

አስተባባሪ ኮሚቴውን ጨምሮ በከተማ ማዕከል እና በክፍለ ከተሞች ያለው ከፍተኛ አመራር የከተማ ግብርና እና የሌማት ትሩፋት ስራዎችን ዉጤታማ ለማድረግ መዋቅራችንንና የተለያዩ የህብረተሰብ ክፍሎችን በማወያየት ያስገኘው ተስፋ ሰጭ ውጤት የሚያበረታታ ነው። ታችኛው መዋቅር ማለትም ብሎክ ድረስ ወርዶ ቀጥተኛ ድጋፍ እያደረገ መሆኑም በጥንካሬ የሚታይ ነው። በከተማችን ያለውን ባለሀብትና መላውን ማህበረሰብ በማስተባበር የተሰሩ ሰው ተኮር ተግባራት በህዝባችን ዉስጥ የመረዳዳትና የመተጋገዝ ባህል እንዲጠናከር እና ወንድማማችነትና እህትማማችነት እንዲጎለብት አድርገዋል። የከተማችንን ሰላምና ደህንነት አስተማማኝ ከማድረግ አኳያ ነዋሪዎችን በማደራጀትና ህዝባዊ ሰራዊቱን በተገቢው መንገድ አሰልጥኖ በማሰማራት ህዝቡ የራሱንና የከተማውን ሰላም እንዲጠብቅ የሚያስችል ጠንካራ የአመራር ስምሪት ሰጥቷል። የከተማችን ህዝብ አንገብጋቢ የሆኑ ኑሮ ውድነትና ሥራ አጥነት ለመቀነስ የተሰራዉ ሥራ ችግሩን በሚመጥን ደረጃ ዉጤት ያመጣንበት ባይሆንም የከፍተኛ አመራሩ ጥረት የሚበረታታ ነው። ህገ ወጥ ግንባታዎችን እና ህገ ወጥ የንግድና የስራ እንቅስቃሴዎችን ወደ ስርዓት ለማስገባት እና የጽንፈኛ ኃይሎችንና የሌሎች ጸረ ሰላም ኃይሎችን እኩይ ተግባር ለማክሸፍ ያደረገው ትግል ውጤት አስመዝግቧል።

በአንጻሩ ደግሞ የህዝብ አገልግሎት አሰጣጥ አለመሻሻል፣ ሌብነትና ጽንፈኝነት አሁንም ያልተሻገርናቸዉ በሁሉም ደረጃ ባለው አመራር የሚታዩ ችግሮች መኖራቸዉ ሲታይ በአዲሱ በጀት አመት ለአመራር ግንባታ ልዩ ትኩረት መስጠት እንዳለብን ያመለክታል። በአመራራችን ውስጥ የአፍራሽ ኃይሎችን አስተሳሰብ የሚጋሩ እንዳሉ ይታወቃል። ሌላው ነዋሪ የሚያነሳው በማስመሰል የጠላትን አጥፊ መልዕክቶች የሚያራግቡ አመራሮች በሁሉም ደረጃ አሉ። በሶሻል ሚዲያዉ ተገቢውን ትግል የማያደርጉና አንዳንዴም አንዳንድ አመራሮች ዛሬም ከብልፅግና

አስተሳሰብ ባፈነገጠ መልኩ ጽንፍ ይዞ የብሄር ጠበቃ መሆንና ብልሽት ዉስጥ ሲገባ ብሔርና አካባቢን መደበቂያ ዋሻ የማድረግ አዝማሚያ ይታያል።

በቅርቡ በተካሄዱ የሼድ እና የመሬት አጠቃቀም የማጥራት ሂደት የተገኙ ውጤቶች በርካታ አመራር ከዜጎች ህይወት መሻሻል ይልቅ የራሱ ወንበር የሚያሳስበው የውሸት ሪፖርትን መኖሪያው ያደረገ እንደሆነ ታይቷል። በአመራሮች መካከል ሰፊ የአፈፃፀም ልዩነት መታየት፣ ተግባራትን አደራጅቶና አስተሳስሮ የመምራት አቅም ማነስ፣ የትግል ውስንነት፣ ህገ ወጥ ግንባታና መሬት ወረራን በሚፈለገዉ ደረጃ ያለመግታት የአመራር ችግሮች አሉብን። በተለይ በታችኛው እርከን ባለው የአመራር ስብስብ ውስጥ የጠባቂነት አስተሳሰብ እና የዉጤታማነት ችግር በስፋት ይስተዋላል። እንደ አጠቃላይ ሲታይም የተቋም ግንባታ ስራችን መሻሻል ያለዉ ቢሆንም አሁንም ያልተሻገርነዉ ችግር ነው።

### 2.5 የመላዉ አባላችን ሁኔታ

በወረዳ 01 ካለዉ 8193 የብልጽግና ፓርቲ አባላት ዉስጥ 7779 የሚሆነዉ አባል በአዲስ ተደረጅቱወለ ። ይህ ሃይል በህዋስ እና በመሰረታዊ ድርጅት ተደራጅቶ በኮንፈረንስና ሌሎች የአቅም ግንባታ መድረኮች በመገኘት እርስ በእርስ ለመገነባባትና የፓርቲያችንን አደረጃጀት ለማጠናከር ጥረት የሚያደርግ ነው። አባላችን ከቁጥር ባለፈ ብልጽግና ፓርቲ በወረዳ 01 ውስጥ ህዝባዊና ተቋማዊ መሰረት እንዲይዝ ከፍተኛ አስተዋፆ እያበረከተ ስለመሆኑ በርካታ ማሳያዎች አሉ።

በከተማችን በተገባደደዉ በጀት ዓመት ለተመዘገቡ የልማት፣ የመልካም አስተዳደርና የአገልግሎት አሰጣጥ ማሻሻል እንዲሁም የተረጋጋ ሰላምና ጸጥታ መስፈን የተጫወተዉ ሚና ተኪ የሌለዉ ነው። አባላችን በመደበኛና ወቅታዊ የንቅናቄ ተግባራት ላይ ከፊት ሆኖ ህዝቡን በማስተባበር፣ በተለያዩ የመንግስትና የህዝብ አደረጃጀት ኮሚቴዎች ውስጥ አመራርና አባል በመሆን የፓርቲያችን የመሪነት ሚና እንዲረጋገጥ ያደረገዉ ጥረትና የተገኘዉ ዉጤት አበረታች እንደሆነ ተገምግሟል። ከወቅታዊ አጀንዳዎች ጋር ተያይዞ በተለያዩ የከተማችን ህብረተሰብ ክፍሎች ዘንድ የሚስተዋሉ ብዥታዎችን ሊቀርፍ የሚችል ግንዛቤ በመፍጠር፣ የማዕድ ማጋራት ስራዎችን በማስተባበር እና ሌሎች ሰዉ ተኮር በጎ ፈቃድ ሥራዎችን በኃላፊነት በመወጣት መላ አባላችን በአርዓያነት ሊጠቀስ የሚችል ዉጤታማ ስራ ሰርቷል። የ60 እና የ90 ቀናት ዕቅድ አፈጻጸም ዉጤታማ እንዲሆን በማድረግ ረገድም የአባላት ተሳትፎ

ላቅ ያለ ነበር፡፡ የከተማችን ነዋሪ ተደራጅቶ የአካባቢውን ሰላምና ፀጥታ በመጠበቅ ባስመዘገበው ስኬት ውስጥ የአባላችን ሚና ግንባር ቀደም ድርሻ አለው፡፡

በአንጻሩ ቁጥሩ ቀላል ያልሆነ አባላችን የጠባቂነት ችግር ያለበት መሆኑ ታይቷል፡፡ ወቅታዊ እና መደበኛ ተግባራትን በራሱ ተነሳሽነትና በፈጠራ ታጅቦ ዉጤት ሊያመጣ በሚችል አግባብ ከመስራት ይልቅ በየደረጃው ያለ አመራርን ጉትጎታ መጠበቅ ይታይበታል፡፡ በአንዳንድ አባላት ዘንድ በብልፅግና ፕሮግራሞች፣ ዕሴቶች እና የብልፅግና እሳቤዎች ዙሪያ በቂ ግንዛቤ ያልጨበጠ ከመሆኑ ጋር ተይይዞ በቀላሉ ለአክራሪነትና ለጽንፈኝነት ተጋላጭነትና ተወሳጅ መሆን ተስተውሏል፡፡ ለዚህ አንዱ መንስዔም የአባላት ምልመላ ስራችን የቁጥር ኮታን ለማሟላት ተብሎ ብቻ በለብለብ የሚፈፀም መሆኑ ነው፡፡ ከአባለት ምልመላ ጥራት እና ፖለቲካ ግንበታ ስራችን መሠራተዊ የሆነ ጉድለት ያለበት ነዉ፡፡

በሚፈጠሩ የአቅም ግንባታ መድረኮች ተሟልቶ አለመገኘት፣ በንባብና በተግባር ራሱን አለማብቃት፣ ዉጤት አልባ መሆን፣ በብሔርና ሃይማኖት ጽንፈኝነት ውስጥ መዘፈቅ፣ ሕገ-ወጥ ተግባራትን አለመከላከልና አንዳንድ ጊዜም ተሳታፊ ሆኖ መገኘት፣ ችግርን ዉጫዊ አድርጎ ማየት፣ በተለያዩ ሱሶች መጠመድ፣ የተሳሳቱ አመለካከቶችንና ተግባራትን ፊት ለፊት ተጋፍጦ አለመታገልና አለማረም አለፍ ሲልም የጽንፍና የተሳሳቱ አመለካከቶች ተጋሪ የመሆን ችግር ይስተዋልበታል፡፡

በመሆኑም በ2016 በጀት አመት አባላትን ከእነዚህ ችግሮች የሚያላቅቅ የፖለቲካ ሥራ መስራት ያስፈልጋል፡፡ አባላችንን ወደ ተጠናከረ የፓርቲና የመንግስት ተልዕኮ ዉስጥ በማስገባት በአዲስ የፖለቲካ ዕይታ እምርታዊ ለዉጥ በከተማችን እንዲመዘገብና በዚህም ሁለንተናዊ ብልጽግና እንዲረጋገጥ ማስቻል ሌላ የሚገበዉ ቁለፍ ተግባር ይሆነል፡፡

### የምሁራንና የመንግስት ሰራተኞች ሁኔታ

ብልጽግና ፓርቲ በፖለቲካ ፕሮግራሙና መተዳደርያ ደንቡ እንዲሁም በአፈፃፀም ደረጃ ምሁራን በአባልነት እንዲካተቱ፤ በመንግስትና በፓርቲዉ የተለያዩ የኃላፊነት ቦታዎች እንዲመደቡና በሌሎች ሀገራዊ ጉዳዮች ዉስጥ አስተዋጾ እንዲያደርጉ ምቹ ሁኔታን ፈጥሯል፡፡ በከተማችንም ይሄው ተግባራዊ እየሆነ የመጣ ሲሆን በቀጣይም ጅምር ስራዎችን አጠናክሮ መቀጠል ያስፈልጋል፡፡ በምሁራን ላይ የምንሰራው የፖለቲካ ስራ ደካማ በመሆኑ የአባላት ቁጥራችን በጣም አነስተኛ እንደሆነ ይታወቃል፡፡ በትምህርት ተቋማት ከሁለተኛ ደረጃ

ትምህርት ቤቶች እስከ ዩኒቨርሲቲዎች ድረስ የፖለቲካና የአደረጃጀት ሥራዎቻችንን ተደራሽነት በማስፋት የሚታዩ ክፍተቶችን ማተስካካልና ምሁራንና በአግባቡ መያዝ ይኖርብናል:: በተቋማት ደረጃም ቢሆን ወሳኝ በሆኑ ሀገራዊ ጉዳዮች ዙሪያ የትምህርት ተቋማት የሀገራዊ ልማት አካል በማድረግ ረገድ ብዙ ርቀት መጓዝ ይኖርብናል::

የፓርቲያችን ተቋም የመገንባት ህልም ያለጠንካራ ሲቪል ሰርቪስ ዳር ሊደርስ አይችልም:: ሲቪል ሰርቪሱ ከነችግሩም ቢሆን በከተማችን እየተመዘገቡ ላሉት ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ስኬቶች የተጫወተው ሚና የሚናቅ አይደለም:: የከተማችን መንግስት ሰራተኞችና ምሁራን የመንግስት ተቋማት አገልግሎት አሰጣጥ የተሻለና ቀልጣፋ እንዲሆን በማድረግ የተገልጋዮችን እርካታ ለማሳደግና የመልካም አስተዳደር ችግሮችን በየተቋሙ ለመፍታት ያደረጉት ጥረት የተሻለ እንደነበር ታይቷል::

ሆኖም መንግስት ሰራተኛው ለከተማችን ለውጥ ማበርከት የሚጠበቅበትን ሚና በሚገባ ተወጥቷል ማለት አይቻልም:: የተሰጣቸዉን ኃላፊነት ወደ ጎን በመተው አሁንም ለተገልጋዩ ህብረተሰብ ተገቢውን ስፍራና ትኩረት የማይሰጡ፣ በመንግስት ሥራ ሰዓት ቢሮ የማይቀመጡና ተገቢዉን አገልግሎት የማይሰጡ ሠራተኞች በየተቋማቱ አሉ:: የሙያና የአገልጋይነት ስነ ምግባር ጉድለት ያለባቸዉ፣ ችግሮችን በባለቤትነት ስሜት የማይፈቱ፣ ሌብነትንና ብልሹ አሰራሮችን እያዩ እንዳላዩ ሆነዉ የሚያልፉ፣ ብሎም ያለ ምልጃ፣ ጉቦና እጅ መንሻ አገልግሎት የማይሰጡ፣ ከብሔር ጽንፈኝነትና ከሀይማኖት አክራሪነት አባዜ ያልተላቀቁ ምሁራንና የመንግስት ሰራተኞች ቁጥር ከፍተኛ ነው::

በሚፈጠሩ መድረኮች በመሳተፍ የፓርቲያችንን ግድፈቶች በግልፅ የሚናገሩ የመኖራቸውን ያክል እንደ ፌስ ቡክና ቲክ ቶክ ባሉ ማህበራዊ ሚድያዎች የሚለቀቁ አፍራሽ መልክዕቶችን በማስተጋባትና በመፃፍ ብልፅግና ፓርቲን ለማሳጣት ተግተው የሚንቀሳቀሱ የመንግስት ሠራተኞችና ምሁራን ቁጥር ቀላል አይደለም:: ባላቸው የእውቀትና የክህሎት ልክና በስራ ልምዳቸው መጠን ራሳቸዉን ለሀገራዊ ችግሮች የመፍትሄ አካል አድርገው በመውሰድ ፋንታ ለሁሉም ነገር መፍትሄ አምጪ መንግስት ነው ብለው የሚያስቡ ብዙ ናቸው::

በሌላ በኩል መንግስት ሰራተኛውም ቢሆን መዋቅራዊና መዋቅራዊ ያልሆኑ ችግሮች ያሉበት ነዉ:: ለመንግስት ሰራተኛው ምቹ የስራ ሁኔታ አለመፈጠሩ እና የአገልግሎት ክፍያው የኑሮ ሁኔታውን የሚመጥንና ለሲቪል ሰርቫንቱ ተነሳሽነት የሚፈጥር አለመሆኑ ተጠቃሽ ችግሮች

ናቸው። በሀገር ደረጃ ያለዉ የዋጋ ግሽበት እያስከተለ ያለዉ የኑሮ ዉድነት ክፉኛ በሆነ መንገድ ሰለባ እየሆነ የሚገኘዉ የህብረተስብ ክፍል አንዱ መንግስት ሠራተኛው ነዉ።

ስለሆነም የመንግስት ሰራተኞችም ሆኑ ምሁራኖቻችን ካላቸዉ ከፍተኛ ተጽዕኖ አኳያ ተቀራርቦ የመስራትና ጥያቄዎቻቸዉን አቅም በፈቀደ መጠን በመመለስ ለሀገር ያላቸዉ አበርክቶ ከፍ እንዲል መስራት ይገባል። በተቻለ መጠን የምሁራን አባላቶቻችንን ቁጥር ለማሳደግ ልዩ ግብ ጥለን መስራት አለብን።

## 2.6 የባለሃብቱና የንግዱ ማህበረሰብ ሁኔታ

የግል ባለሃብቱ ከጅምሩ የፓርቲያችን ደጋፊ መሆኑን ሲያሳይ የቆየ የህብረተሠብ ክፍል ነዉ። በተለይም ፓርቲያችን የሚከተለዉ የአካታችነት መርህ በተግባርም እያረጋገጠ የመጣ ስለሆነ በግል ባለሃብቱ ዘንድ ጥሩ ስሜትና ተስፋ እየሠጠዉ ይገኛል። ባለሃብቱ ሀገራችን አሁን ያለችበት ችግር ለመቅረፍ በሚደረገዉ ርብርብ የበኩሉን ሀገራዊ ግዳጅ እየተወጣ ይገኛል። በከተማችን ለሚተገበሩ የልማት ፕሮጀክቶች፣ ሰው ተኮር ለሆኑ የበጎ አድራጎት ስራዎች ከፍተኛ የሃብት ድጋፍ እያደረገ ይገኛል።

አጠቃላይ የንግዱ ማህበረሰብም በከተማችን የልማት ስራዎች ላይ ሀብት በመለገስ፣ ሰዉ ተኮር የልማትና በጎ አድራጎት ተግባራት ላይ በመሳተፍ የሚያርጉት አበርክቶ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠዉ ነው። በከተማችን ዉስጥ በሚካሄዱ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ልማት እንቅስቃሴዎች ውስጥም የንግዱ ማህበረሰብ ሚና ጉልህ በመሆኑ በህግ አግባብ ብቻ የሚንቀሳቀሱ፣ የምርትና ሸቀጥ አቅርቦት ዕጥረት እንዳይባባስ የሚሰሩና ሸማቹን ህብረተሰብ በቅንነትና በታማኝነት የሚያገለግሉ ነጋዴዎችን በርካታ ናቸው። በአንጻሩ አንዳንድ ነጋዴዎች ምርት በመደበቅ ያለአግባብ ለመክበር በመፈለግ የገበያ አለመረጋጋትና የኑሮ ውድነትን በማባባስ በህብረተሰቡ ላይ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ጫና እንዲፈጠር ያደርጋሉ። በህገ ወጥ ተግባራት ላይ በማሳተፍ የገበያ ሥርዓት የሚያዛቡ፣ ምርት የሚሰዉሩና ለሸቀጥ እጥረት መንስኤ የሚሆኑ ነጋዴዎችም ቁጥራቸዉ ቀላል አይደለም።

ፓርቲያችን በአንዳንድ ጉዳዮች ላይ ከባለሃብቶችና ከነጋዴ ማህበረሰብ ጋር ተቀራርቦ ከመወያየትና አስተዋፆአቸውን ከመጠየቅ ባለፈ ወደ ፓርቲያችን በአባልነት የሚቀላቀሉበት ሁኔታ ላይ በስፋት አልሰራብትም። ሀገሩን የሚወድ፤ ማህበራዊ ሃላፊነቱን በአግባቡ የሚወጣና

ለህዝቡ ጥቅም የሚሠራ ባለሀብት እንዲበራከት የተሠራዉ ሥራ በቂ አይደለም፡፡ ባለሃብቶችና የነጋዴው ማህበረሰብ እንደማንኛውም የከተማችን ነዋሪ ብልፅግናን የመቀላቀል መብት አላቸው፡፡ ይህ ደግሞ ከፓርቲያችን ሁሉን አቃፊነት ባህሪይ የሚመነጭ ነው፡፡ በሌላ በኩል የእነዚህ የህብረተሰብ ክፍሎች ወደ ፓርቲ መግባት በአባላት መዋጮ የምናገኘውን ገቢ በከፍተኛ መጠን ያሳድገዋል፡፡ በዚህ ረገድ እስካሁን ጥቂት ጅምር ስራዎች ቢኖሩም ትኩረት ያልተሰጠው በመሆኑ በአዲሱ አመት ከፍተኛ ለውጥ የምናመጣበት መሆን ይኖርበታል፡፡

በመደበኛነትም በባለሀብቱና በንግዱ ማህበረሰባችን ዘንድ የሚታዩ አዎንታዊ ዝንባሌዎችንና በጎ አስተዋጾአቸዉን ማጎልበትና አሉታዊ ዝንባሌዎችንና ህገ ወጥ እንቅስቃሴዎችን ማስቀረት በሚያስችል ሁኔታ የቅርብ ድጋፍና ክትትል በማድረግ ማረምና በከተማዉ ሁለንተናዊ ዕድገትና የብልጽግና ጉዞአችን ሂደት የሚያበረክቱትን አስተዋፅኦ እንዲያሳድጉ ማድረግ ይኖርብናል፡፡ ልክ በሌሎች የህብረተሰብ ክፍሎች እንዳደረግነው ሁሉ የንግዱ ማህበረሰብ አባላትን ከወረዳ ጀምሮ የሚያሳትፍ የንቅናቄ መድረክ ማዘጋጀት ይጠበቅብናል፡፡

## 2.7 የ1ኛ መደበኛ ጉባኤ ዉሳኔዎችና አቅጣጫዎች እንደመነሻ

የብልፅግና ፓርቲ  አንደኛ መደበኛ ጉባኤ  ካስቀመጣቸው አቅጣጫዎችና ውሳኔዎች መካከል በከተማችን ተግባራዊ ሊደረጉ የሚገባቸውን ተግባራት ለመፈጸም ትኩረት ተሰጥቶ ሲሰራ ቆይቷል፡፡ ጉባዔው ካስተላለፋቸው ውሳኔዎች እና በከተማችንም ርብርብ ከተደረገባቸው ዉስጥ የተቋማት ግንባታ፣ የውስጠ ፓርቲ ጤንነት፣ የስራ እድል ፈጠራ፣ የኑሮ ውድነሰት መከላከል፣ የህዝብ ቅሬታዎችንና የመልካም አስተዳደር ችግሮችን መፍታት፣ የዘላቂ ሰላም ግንባታ፣ የአረንጓዴ አሻራ ልማት፣ ብዝሀ ኢኮኖሚ ልማት ይገኙበታል፡፡

በተለያየ ጊዜ ለሰላም መደፍረስ ምክንያት እየሆነ ያለው የብሄርና የሃይማኖት ጽንፈኝነትና አክራሪነትን ለመታገል የሚያስችል ውይይት በፓርቲ መዋቅር እና በመላው ህዝባችን ውስጥ በተደጋጋሚ እንዲካሄዱ ተደርጓል፡፡ በመዋቅራችን ውስጥ የሚታይ የአመለካከት ብልሽት ላይ መተጋገል የተካሄደ ሲሆን እንደ አስፈላጊነቱም የእርምት እርምጃዎች በተለያየ ደረጃ ተወስደዋል፡፡ አመራራችን አሁንም ከችግሩ የፀዳ ነው ማለት ባይቻልም ጽንፈኝነትና አክራሪነትን የስርዓታችን አደጋ መሆኑ ላይ ግልፀኝነት መፈጠሩ፣ ችግሩን ሳይሸፋፈን መተጋገል መቻሉ እና ሁለት ቦታ እየረገጡ ፓርቲ ውስጥ መቆየት እንደማይቻል ቁርጠኛ አቋም መያዙ ለቀጣይ ስራ እንደ መልካም መሰረት ተደርጎ የሚወሰድ ነው፡፡

የመልካም አስተዳደር ችግሮችን በተለይም ከሌብነትና ከስርቆት ጋር በቀጥታ የተያያዙ ህዝቡን ያማረሩ ጉዳዮችን ለመፍታት በከተማችን በሁሉም መዋቅር የመወያያ ሰነድ ተዘጋጅቶ አባሉና ህዝቡ እንዲመክርበት ማድረግ ተችሏል። ከመድረክ ባለፈም ህዝቡ ጥቆማ የሚሰጥባቸውን ስልቶችን በመንደፍ ነዋሪውን ያሳተፈ የፀረ ሌብነት ትግል ተካሂዷል። ከመሬትና የንግድ ስርዓቱ ጋር በተያያዘ እጃቸው ያለበት አመራሮችን በደረስንበት ልክ በሁሉም ደረጃ እርምጃ እንዲወሰድባቸው ተደርጓል። ከሼድ አሰጣጥና አጠቃቀም ጋር በተያያዘም ተገቢውን የማጥራት ስራ በመስራት መረጃ በማዛባት፣ ተገቢ ያልሆነ አሰራር በመከተል ከአሰራር እና ከመመርያ ውጪ በመስጠት የቅሬታ ምንጭ በመሆን የተለዩ አመራሮችና ባለሙያዎች ላይ እርምጃ እየተወሰደ ይገኛል። ባለፉት አመታት የነበሩ ችግሮችን በማይደግም መልኩና ወጣቶችና ሴቶችም ማዕከል ላደረገ የስራ እድል ፈጠራ በሚያግዝ ሁኔ ሼዶችን የማከፋፈል ስራም ተጀምሯል።

የከተማችን ነዋሪ ሀገራዊና አለም አቀፋዊ ገፅታም ባለው የኑሮ ውድነት እየተሰቃየ እንደሚገኝ ግልፅ ነው። በተለይ አነስተኛ ገቢ ያለው ነዋሪና የመንግስት ሰራተኛው በቤት ኪራይ፣ በትራንስፖርት እጥረት፣ በመሰረታዊ ሸቀጦች እጥረትና መሰል ችግሮች ክፉኛ ተጎድቷል። ጉባዔያችን ባስቀመጣቸው አቅጣጫዎች መሰረት በፓርቲና በመንግስት አመራሩ ቅንጅት ችግሮቹን ለማቃለል ጥረቶች ተደርገዋል።

አሁን በግንባታ ላይ የሚገኙ ቤቶችን ከማፋጠን በተጨማሪ ዜጎች እንደየአቅማቸው ባጠረ ጊዜ የቤት አማራጮችን የሚያኙባቸው የተለያየ ስልቶች ተቀርፀዋል። በከተማው አስተዳደር ከፍተኛ ወጪ ዘመናዊ አውቶቡሶችን በመግዛት የትራንስፖርት ችግሩን ለማቃለል ጥረት ተደርጓል። ዘይትና ስኳርን ጨምሮ የተለያዩ መሰረታዊ ፍጆታዎችን በሸማቾች ማህበራት በኩል ማቅረብ ተችሏል። በዚህ ሂደት የመጡ አዎንታዊ ለውጦች ቢኖሩም እንደ ስንዴና ጤፍ ባሉት የምግብ እህሎች ላይ ደግሞ በተለያዩ ተገቢና ተገቢ ባልሆኑ ምክንያቶች የተነሳ እጥረት በማጋጠሙ ህዝባችን አሁን በችግር ውስጥ ይገኛል። ይህን ችግር ለመሻገር በፓርቲ የሚመራ የኑሮ ውድነት መከላከል ግብረ ሃይል ተቋቁሞ አቅርቦቶቹን ለማሳደግና ዘላቂ መፍትሄዎችን ለማበጀት እየሰራ ይገኛል። በ2014 ጀምሮ በንቅናቄ ስንተገብረው የመጣነውን የከተማ ግብርና ተቋማዊ አሰራር ይዞ እንዲቀጥል በማድረግ በኑሮ ውድነት መከላከሉ ላይ አይነተኛ ሚና እንዲኖረው ተደርጓል። እነዚህ የኑሮ ውድነት መከላከል ስራዎች ከስራ እድል ፈጠራ ጋር

ተቀናጅተው እየተሰራባቸው ቢገኝም ችግሩ አሁንም የከፋ በመሆኑ በዚህ አመትም የፓርቲና የመንግስት ስራዎቻችን ማዕከል ሆኖ መቀጠል ይገባዋል፡፡

የውስጠ-ፓርቲ ፖለቲካዊ ጤንነት መጓደል፣ የአመራርና አባላት ጥራት ችግር በፓርቲያችን ብሎም በህዝባችን ላይ ያስከተለው አሉታዊ ተፅዕኖ ገምግሞ አንደኛ ጉባዔያችን ለውጡን ማጽናት የሚለውን አቅጣጫ መሰረት ያደረጉ አቅጣጫዎችን አስቀምጧል፡፡ እንደ ከተማም ለውጡ በባህሪው ነባሩን የተዛባ የፖለቲካ ትርክትና አካሄድ በመቀየር እና የሕዝብን ፍላጎት በሚያሟላ መልኩ ለማስተካከል በመደመር መንገድ አዲስ የፖለቲካ እይታ፣ አካሄድና አደረጃጀት ማለማመድ፣ ማስረጽ እና ማዋሐድ የሚፈልግ ረጅም ሂደት መሆኑ ላይ በመተማመን ወደተግባር ገብተናል፡፡ በየጊዜው በስራ አስፈፃሚ ኮሚቴ፣ በፓርቲ ዋና ፅ/ቤትና በከተማ ማዕከል ደረጃ እየተቀረፁ ውይይት የሚደረግባቸው አጀንዳዎች በአመራሩና በአባሉ መካከል የዓላማ እና የተግባር አንድነትን ለማጠናከር፣ የውስጠ-ድርጅት ዴሞክራሲን ለማጎልበት በአጠቃላይ ለፓርቲ ጤንነት መጠበቅና ለተቋም ግንባታ ከፍተኛ ድጋፍ ያደረጉ ሲሆን ተልዕኮው ቀጣይነት የሚጠይቅ መሆኑን ታሳቢ ያደረጉ ስራዎች በዚህ በጀት አመትም መተግበር አለባቸው፡፡ በተጨማሪም ለመድብለ ፓርቲ ሥርዓት ካላቸው ሁለንተናዊ አስተዋጽኦ አንጻር ጉባዔው ባስቀመጠው አቅጣጫ መሰረት ከተፎካካሪ ፓርቲዎቹ ጋር በሀገራዊ ጉዳዮች ላይ በጋራ እየሰራን ሲሆን በቀጣይም በከተማዋ ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ አጀንዳዎች ላይ ከተፎካካሪ ፓርቲዎች ጋር በትብብር ሊሰራ ይገባል፡፡

የ2017 በጀት አመት የጉባዔ ውሳኔዎች የትግበራ ጊዜ አማካኝ ወቅት ላይ የሚያርፍ እንደመሆኑ መጠን በዚህ አመት ከውሳኔዎቹ አንፃር ያለንበትን ደረጃ ገምግሞ ጥንካሬዎቹን ይበልጥ ማጎልበት፤ ጉድለቶችን ደግሞ ማስተካከልና ቀሪ ተግባራት በቀሩት ጊዜያቶች የሚፈፀሙትን ትልም ማስቀመት ይጠይቃል፡፡ ስለሆነም የብልጽግና ፓርቲ 1ኛ መደበኛ ጉባኤ ዉሳኔዎችና አቅጣጫዎች ለ2017 በጀት ዓመት ዕቅድ እንደ መነሻ ተወስዷል፡፡

### 2.8 ምርጫ እንደ መነሻ

በ2013 ዓም በተካሄደው አገራዊ እና ክልላዊ ምርጫ እንድ ፓርቲ ለውድድር ስንቀርብ ብልጽግና ቢመረጥ ሊሰራቸው የሚችል እን የፓርቲያችንን የወደፊት ራዕይ በሚያሳይ መልኩ የተዘጋጀውን ማንፌስቶ እንደከተማ በሚገባ ለመራጩ ህዝብ በማስተዋወቅ ከህዝቡ ጋር የቃልኪዳን ውል ፈጽመናል፡፡ ፓርቲያችን ከዓላማው ጀምሮ ኢኮኖሚያዊ ፤ፖለቲካዊ እና

ማህበራዊ ሁኔታዎችን በመዘርዘር ህዝቡ የሚያነሳቸውን የመልካም አስተዳደር ችግሮችን በመጥቀስ፣ በየደረጃው ያለውን ብልሹ አሰራር እና የሌብነት ሁኔታዎችን ትግል በማድረግ እነዚህን ችግሮችን ደረጃ በደረጃ እፈታለሁ ማለቱ ይታወሳል፡፡

በመሆኑም ከምርጫው ማግስት ጀምሮ ባሉን አፈጻጸሞች ላይ ማኒፌስቷችንን መነሻ እና ታሳቢ በማድረግ ከቃላችን የተጓደሉ ጉዳዮች ካሉ ክፍተቶችን ሊያርሙ የሚችሉ ስራዎችን መስራት ይጠበቅብናል፡፡ ህዝቡ በ2013 ምርጫ ድምጹን ለፓርቲያችን ሲሰጥ ሁሉም ነገር በአንድ የምርጫ ዘመን ይፈታልኛል ብሎ እንዳልሆነ ይታወቃል፡፡ ሆኖም ያሉትን ችግሮች ከወዲሁ እያስተካከልን በህዝቡ ዘንድ ቅቡልነትን የማግኘት ስራዎች መስራት ወሳኝ ነው፡፡ ከዚሁ ጎን ለጎን በተግባር የፈፀምናቸውን ቃሎች ደግሞ ለህዝባችን በመግለጽ እየተማመኑ መሄድ በሀገራችን የተለመደውን ለምርጫ የተገባው ቃል ከምርጫ በኃላ አይፈጸምም የሚል ትርክት ለመስበርና ለቀጣዩ የአካባቢ ምርጫ ምቹ መስፈንጠሪያ ለመፍጠር አስፈላጊ ነው፡፡

በአዲስ አበባ ከተማ በ2017 ዓ.ም የሚካሄደውን የአካባቢ ምርጫ ላይ ዲሞክራሲያዊ እና በህዝብ ዘንድ ተዓማኒነት ያተረፈ፤ መላው የከተማችን ነዋሪ በነቂስ ወጥቶ የሚሳተፍበት እንዲሁም ብልጽግና በአብለጫ ድምጽ የሚያሸንፍበት እንዲሆን ባለፈው ምርጫ የታዩ ጠንካራ ልምዶችን ማስቀጠል እንዲሁም ድክመቶችን ማረም አስፈላጊ በመሆኑ የምርጫ ሁኔታን ለ2016 በጀት አመት የእቅድ መነሻ ማድረግ ተገቢ ይሆናል፡፡

በጥቅሉ ሲታይ በ2013 ዓ.ም አለም የመሰከረለት በአፍሪካ የተሳካለት ምርጫ አድርገናል፡፡ በመጪው አመት ከዛም የተሻለ ውጤት ለማሳካት መስራት ይጠበቅብናል፡፡ የምርጫ እንቅስቃሴያችን ፓርቲው ከማዕከል በሚያወጣው የምርጫ ማስፈጸሚያ ዕቅድ እና ስትራቴጂ መሰረት የሚመራ ቢሆንም እንደከተማ ቀድመን ማከናወን ያሉብንን ተግባራት በግዜ የለኝም ስሜት ከወዲሁ መፈፀም ይኖርብናል፡፡ ለአብነት ከሲቪል ማህበራት እና ከተፎካካሪ ፓርቲዎች ጋር ያለንን ትስስር ከወዲሁ ማጠናከር አስፈላጊ ይሆናል፡፡

### 2.9 የ2016 በጀት ዓመት ዕቅድ አፈጻጸም እንደ መነሻ

በ2016 በጀት ዓመት በከተማችን ደረጃ የተለያዩ የድርጅትና የፖለቲካ ተግባራትን አቅደን በዉጤታማነት መፈጸም የተቻለ ሲሆን የተወሰኑ የከተማችንን ሜጋ ፕሮጀክቶች አጠናቀን

ቀሪዎቹን በፈጣን ሂደት ውስጥ ያስገባንበት ነው፡፡ የ2016 በጀት ዋና ዋና ተግባራት አፈጻጸም ለ2017ዓ.ም ለዕቅድ መነሻ እንዲሆን እንደሚከተለዉ ቀርቧል፡፡

## 2.10 አባላትን የተመለከቱ ስራዎች ያሉበት ሁኔታ

ጠንካራ የፓርቲ ተቋም ለመፍጠር አዳዲስ እጩ አባላት የፓርቲውን ህገ ደንብ ላይ ተወያይተውና አምነተውበት እንዲሁም ተልዕኳቸውን አውቀው እንዲገቡ ማድረግ ያስፈልጋል፡፡ ባለፉት አመታት በዚህ ረገድ ሰፊ ክፍተቶች እንደነበሩብን ይታወቃል፡፡ ይህን ችግር ለመቅረፍ በተጠናቀቀው በጀት አመት ጠንካራ ክትትልና ድጋፍ በመደረጉ አዎንታዊ ለውጦች አሉ፡፡ ሆኖም አሁንም የተቀመጠውን አቅጣጫ ተቀብሎ መፈፀም ላይ ክፍተት አለብን፡፡ ምንም እንኳን አሁን ላይ አጠቃላይ የአባል መሰረታችን እየሰፋ ሄዶ 8193 አባል ቢኖረንም ማህበራዊ መሰረቶችን ከማስፋት አንፃር ጉድለት አለብን፡፡ ለምሳሌ ባለሃብቶችን፣ ወጣቶችንና ምሁራንን የመመልመል ሥራ ላይ ችግር እንዳለ ገምግመናል፡፡

የመረጃ አያያዝ ስርዓቱን በተመለከተ በአምስት ደረጃዎች ማለትም ካቢኔ፣ ፓርቲ ጽ/ቤት፣ ተቋም ኃላፊዎች፣ ምክር ቤትና በሌሎች የሹመት ደረጃዎች ተለይቶ በከተማ፣ በክፍለ ከተማ እና በወረዳ ያለው የአመራር መረጃ በሀርድና ሶፍት ኮፒ ተደራጅቶ እንዲያዝ ተደርጓል፤ ለዋና የፓርቲያችን ጽህፈት ቤትም እንዲተላለፍ ተደርጓል፡፡ በተመሳሳይ አዳዲስ የሚገቡ አባላትና የታችኛው መዋቅር ማለትም የመሰረታዊ ድርጅትና ህዋሳት አመራሮች እና የአባላት መረጃ በዳታ ቤዝ በአግባቡ ተደራጅቷል፡፡ ወደ ዳታቤዝ ያልገቡትን ለይቶ በፍጥነት ማጠናቀቅ ይጠይቃል፡፡

በተጨማሪ አሁንም ከአባላት መረጃ አያያዝ ያሉ የቁጥር መዋዠቅ እና የእርስ በርስ መጣረስ፤ የመረጃ መጥፋት እና የውሸት ሪፖርት የመሳሰሉ ችግሮች ይስተዋላሉ፡፡ የአመራርና የአባላት መረጃ አያያዝ ሥርዓት ለማሻሻል የተሰሩ ሥራዎችና አዲስ ሶፍትዌሮችን ለማልማት በክፍለ ከተሞች ጭምር የተከናወኑት ተግባራት አበረታች ናቸው፡፡ እስካሁን በተከናወኑ የሶፍትዌር ልማቶች ላይ አስፈላጊ የሆኑ ማስተካከያዎችን በማድረግ፣ ስራችንን በተሻለ ሁኔታ የሚያሳልጡልንን በመምረጥ፣ እንደ ፓርቲ ወጥ የሆነ የመረጃ ቋትና የአሰራር ስርዓት መዘርጋትና በሁሉም ደረጃ እንደከተማ ወጥ የሆነና ሁሉንም መረጀዎቻችን መደራጀት የሚያስችል ቴክኖሎጅ በመልማት ከችግሮቹ መዉጣት ይኖርብናል፡፡

## 2.11 ተቋማዊ አሰራርና አደረጃጀት ከማጠናከር አንፃር

ብልጽግናን ማስቀጠል የሚችል ጠንካራ የፓርቲ አሰራርና አደረጃጀት ለመፍጠር የተለያዩ ስራዎች ተሰርተዋል። ተቋማቶችና አደረጃጀቶችን እስከ ታች ድረስ (ብሎክ እና ህዋስ) በማደራጀት የስምሪት ማዕከል ማድረግ መቻሉ፣ የተቀናጀ የክትትል ድጋፍ፣ ግምገማና ግብረ መልስ ስርዓት እየተጠናከረ መምጣቱ በጥንካሬ የሚታዩ ናቸው። ይህ እንደተጠበቀ ሆኖ ተሞክሮዎችን ቀምሮ የመያዝ እና የማስፋት እንዲሁም የተቋማትና መዋቅሮቻችንን ውጤታማነት ማረጋገጥና የመፈፀም አቅም ማሳደግን ገና የሚቀረን እንደሆነ ተገምግሟል። መተዳደርያ ደንብና ፕሮግራምን ጨምሮ በፓርቲያችን ዋና ፅ/ቤት የተዘጋጁ መመሪያዎችን እስከታችኛው መዋቅር የማድረስ ስራ ተሰርቷል። ተደራሽነታቸውንና ግንዛቤን ማስፋት ላይ በ2016 በጀት አመት በስፋት መሰራት ይኖርበታል።

ከሰው ሃይል ስምሪትና ውጤታማነት አንጻር የነበሩንን ችግሮች ግምት ውስጥ ያስገባ አዲስ መዋቅር ተዘጋጅቶ የመጣ በመሆኑ የሰው ኃይል ስምሪት ላይ ጥራት ያለው ስራ መስራት፣ በመዋቅሩ ለሚመደበው አመራርና ባለሙያ በአዳዲስ የለውጥ አሰራሮችና ዘመናዊ ቴክኖሎጂ አጠቃቀም ላይ በቂ ግንዛቤ እና ዕውቀት ማስጨበጥ ያስፈልጋል።

## 2.12 የ2017 ዕቅድ ዋና ዋና ታሳቢዎች

በ2016 በጀት ዓመት የፓርቲንና የመንግስትን ዕቅድ ስናቅድ በአፈጻጸም ሂደት አዎንታዊም ሆነ አሉታዊ ተጽዕኖ የማሳረፍ ኃይል ያላቸዉ ታሳቢዎች ተለይተዉ የዕቅዳችን አካል እንዲሆኑ ተደርገዋል። አንዳንዶቹ ታሳቢዎች በ2016 በጀት ዓመት የተያዙ፣ ሳይቀየሩ የተሻገሩና አሁንም ተጽዕኖ ማሳረፍ የሚችሉ ናቸዉ። ሌሎቹ ደግሞ ዓለማቀፋዊ፣ ቀጠናዊና ሀገራዊ ተለዋዋጭ ሁኔታዎች የፈጠሯቸዉ አዳዲስ ታሳቢዎች ናቸዉ።

### 2.12.1 ለዉጡንና የለውጡን ቀጣይነት ማረጋገጥ

ለዉጡንና የለውጡን ቀጣይነት ማረጋገጥ አሁንም የሚቀጥል ታሳቢ ሲሆን ከዚህ አንጻር ባለፉት አመታት ያስመዘገብናቸውን ውጤቶች ይበልጥ አጠናክረን፤ ፈተናዎችን ቀንሰን የለውጡ ፍሬ የሆነውን ብልጽግና ህዝባዊና ተቋማዊ መሰረት ያለው በእሳቤና በተግባር ውጤታማነት እና በዲስፕሊን ጠንካራ ፓርቲ የማድረግ ጉዳይ ትልቁን ስፍራ የሚይዝ የአዲስ ዕቅድ ታሳቢ ነው። ስለሆነም ስለ ለውጥና የለውጡ ቀጣይነት ስናስብ ቀደም ብሎ መምጣት

ያለበት የፓርቲያችን ጥንካሬና ተቋማዊ ቁመና ስለሚሆን በ2017 በጀት ዓመት ጠንካራና የማድረግ አቅም ያለዉና በአሳቤ፣ በአሰራር፣ በአደረጃጀት፣ በሰዉ ኃይልና በቴክኖሎጂ የዳበረ የፓርቲ ተቋም መገንባት ላይ በትኩራት መስራት ይጠበቅብናል።

### 2.12.2 የተልዕኮ ግልፀኝነትና የፓርቲ ስብዕና ግንባታ

አመራሩና አባላት በፓርቲያችን መሰረታዊያን፣ እሳቤዎች፣ እሴቶች፣ መርሆዎችና ዓላማ ላይ የጠራ ግንዛቤ፣ ቁርጠኝነትና እምነት እንዲያጎለብቱ የሚያደርግ ተከታታይ የአቅም ግንባታ ሥልጠና እንዲያገኙ በትኩረት ይሰራል። ስለሆነም የአስተሳሰብ ጥራት ተላብሶ የተግባር ዉጤታማነትን የሚያረጋግጥ፣ ፈተናዎችን ወደ ዕድል የሚቀይር፣ ከፈተና መዉጫ ብልሃቶችን እየቀየሰ መምራት የሚችል፣ የብሔር ጽንፈኝነትንና የሀይማኖት አክራሪነትን አምሮ የሚታገል፣ የተልዕኮ ግልጽነትና የፓርቲ ስብዕና የተላበሰ የአመራር ሥርዓት የዕቅዳችን ቁልፍ ታሳቢ ተደርጎ የርብርብ ማዕከል ይሆናል።

የፓርቲ ስብዕና ሌላዉ ማዕከል በአዲስ የፖለቲካ ዕይታ ሀገራዊ እመርታ ማስመዝገብ ሲሆን ይህም ከብልጽግና ፓርቲ ትውልድ ግንባታ ሥራችን ጋር በእጅጉ የተቆራኘ ነዉ። በፓርቲዉ ራዕይ፣ ዓላማና ግቦች ላይ የጋራ አስተሳሰብ የፈጠረ ብቃት ያለዉ አመራርና አባል በመፍጠር በመዋቅራችን ዉስጥ የባለቤትነትና የማድረግ አቅም ማጎልበት ያስፈልጋል። በህዝብ ዉስጥም በተመሳሳይ ሁኔታ በአመራረት፣ በአመጋገብና በቁጠባ የባህል ሽግግር የሚያስከትል የአስተሳሰብ ለዉጥ እንዲመጣ ድጋፍ እንዲሰጥ ማድረግ ሌላ ስራችን ይሆናል።

### 2.12.4 የአገልግሎት ጥራትና ተደራሽነትን ማሻሻል

የመንግስት ተቋማት አገልግሎት ጥራትና ተደራሽነት ማሻሻል ሌላዉ የ2017 በጀት ዓመት ዕቅድ ታሳቢ ነው። በከተማችን የህብረተሰቡን ተጠቃሚነት የሚያጎብቱና የአዲስ አበባን የኢትዮጵያ ብልጽግና ተምሳሌትነት የሚያረጋግጡ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ልማት ሥራዎች እየተሰሩ ይገኛል። በሌላ በኩል ወሳኝ በሆኑና እንደ መሬት፣ ቤቶች፣ ወሳኝ ኩነት፣ ንግድ፣ ግዥ፣ ገቢ አሰባሰብ፣ የግንባታ ፍቃድና ቁጥጥር አገልግሎት ሰጪ ተቋማት በጠራራ ፀሐይ እጅግ ከፍተኛ መጠን ያለዉ የአገልግሎት ጉቦ የሚጠየቅባቸዉ ሆነዋል። በእነዚህ አካባቢዎች ጉቦ፣ ስርቆት እና የተደራጀ ሌብነት አድማሱን እያሰፈ በመምጣት የመንግስትን ሥርዓት እስከ መፈታተን ደርሷል። ዋና መገለጫዉም ውሳኔ ያለመስጠት፣ ጉዳይ ማጓተት፣ በጉቦና ምልጃ

መሥራት፣ በትውውቅና ዝምድና ማስተናገድ እና በኔትወርክና ማናለብኝነት በመንግስት ሥራ ሰዓት ቢሮ ዘግቶ በመዉጣት ዜጎችን ማንኳሰስና ማመናጨቅ ሆኗል። ይህንን ሁኔታ የሚቀይር ርምጃ በመዉሰድ መሰረታዊ ለውጥ ማምጣት የወቅቱ ፈተና በመሆኑ የመንግስትን አገልግሎት በዘመናዊ ቴክኖሎጂ አስደግፎ በማሻሻል ከአድሎ፣ ከብልሹ አሰራር እና ሌብነት ማጽዳት የሚያስችል ተጠያቂነት ማረጋገጥ የዕቅዱ ታሳቢ ተደርጓል።

### 2.12.5 ስራ እድል ፈጠራና የኑሮ ውድነትን መከላከል

የምርቶችና ሸቀጦች ዋጋ ንረትና የገበያ አለመረጋጋት ችግሮችን በማስወገድ የህብረተሰቡን የኑሮ ሁኔታ ማሻሻልም የ2017 በጀት ዓመት ታሳቢ ነዉ። በከተማችን ያለዉ ሥራ አጥነትና ኑሮ ውድነት በዋናነት በዝቅተኛ የኑሮ ደረጃ ላይ የሚገኘዉን የህብረተሰብ ክፍል ድህነትና ጉስቁልና እያባባሰዉ ይገኛል። ይህን ሁኔታ ለመቀየር ሁሉንም የልማት አቅሞች አሟጦ መጠቀም የሚያስችል ስልት መቀየስ ይኖርብናል።

ሌላው በነዋሪው ዘንድ ከፍተኛ ቅሬታ እያስነሳ ያለው የመኖሪያ ቤት እጦት ችግር ነው። ይህንን ችግር ለመቅረፍ ከተማ አስተዳደሩ ከፍተኛ ርብርብ ሲያደርግ የቆየ ቢሆንም ከነበረው ከፍተኛ የቤት ፈላጊዎች ቁጥር አኳያ የከተማችንን የቤት አቅርቦት ችግር መቅረፍ አልተቻለም። በአሰራር ችግርም ቤቶች ያለአግባብ የተያዙበትን ሁኔታ በማስተካከል ፍትሃዊ ተጠቃሚነትን ለማረጋገጥ እየተሠራ ያለውን ጅምር ስራ በማጠናከር እንዲሁም የተጀመሩትን ሰፋፊ የቤት ግንባታ ፕሮጀክቶችን በማጠናከር የነዋሪዎችን ፍላጎትና አቅም ባገናዘበ ሁኔታ ተጠቃሚ ማድረግ ያስፈልጋል። የምርትና ሸቀጥ አቅርቦት በማሻሻል፣ የከተማ ግብርና በማስፋፋት፣ ሰዉ ሰራሽ የዋጋ ንረትና የኑሮ ውድነት መንስኤዎችን በማስወገድ፣ ለዜጎች በቂ የስራ ዕድልና የገቢ አማራጮችን መሰረት በማስፋት እና በህብረሰቡ ዘንድ የባህል ሽግግር በማምጣት ኑሮ ዉድነትን መቀነስ የዕቅዱ ታሳቢ ሆኗል።

የከተማችን ነዋሪ ሌላዉ ተግዳሮት የትራንስፖርት አገልግሎት ችግር ስለሆነ ይህንን ችግር ለመቅረፍ ከተማ አስተዳደሩ ያሉትን የህዝብ ትራንስፖርት አማራጮችን በውጤታማነት ከማሰማራት በተጓዳኝ ለልማት ከሚውል በጀት ቀንሶ አጋዥ ባሶችን በመከራየትና አዳዲሲ ባሶችን በመግዛት ችግሩን ለማቃለል ጥረት አድርጓል። ነገር ግን አሁንም ችግሩ ስላልተቀረፈ በቀጣይ የህዝብ ትራንስፖርቱን አድማስ በማስፋትና የመንገድ መሠረተ ልማት ተደራሽነት በማፋጠን ህዝቡን የሚመጥን የትራንስፖርት አገልግሎት ተደራሽ ማድረግ ይጠይቃል።

### 2.12.6 የጉባኤ ዉሳኔዎችና አቅጣጫዎችን መፈጸም

የጉባኤ ዉሳኔና አቅጣጫዎችን በጥብቅ ዲሲፕሊን መፈጸም ሌላዉ ወሳኝ የዕቅዳችን ታሳቢ ነዉ። በጽንፈኝነትና በአክራሪነት የሚገለጹ ፖለቲካዊ ስብራቶችን መጠገን የሚያስችል ድልድይ በመስራት ጠቃሚ የባህል ለዉጥና ሽግግር በማምጣት የበለጸገችና ጠንካራ ሀገርና ከተማ ለመገንባት የመጀመሪያው ታሪካዊ የፓርቲያችን ጉባኤ ያስመቀመጣቸዉን ዉሳኔዎችና አቅጣጫዎችን አስቀምጧል። እነዚህ ውሳኔዎች ተከትሎ የ60 እና የ90 ቀን ዕቅድ በማዘጋጀት የአመራርና የአባላት ብሎም የህዝቡን ተሳትፎና ባለቤትነት ባማከለ አግባብ የያዝናቸውን ግቦች ለመፈጸም ተረባርበን የተሻሉ ውጤቶችን አስመዝግበናል። ዘንድሮም በተደራጀ የህዝብ ንቅናቄና የአመራር ቁርጠኝነት ተግባራዊ ለማድረግ ከመቼዉም ጊዜ በተሻሌ መንቀሳቀስ ይኖርብናል።

## 2. ክፍል ሁለት

### 3.1 የእቅዱ አላማ

በ2017 ዓ.ም በየደረጃዉ የሚገኘዉ የፓርቲ መዋቅር ተፅእኖ የመፍጠር አቅሙ የዳበረ፣ ውስጣዊ ጥራት ያለው፣ ጠንካራና የተዋሀደ፣ተቋማዊ የፓርቲ አደረጃጀት በመገንባት ተልዕኮውን በተደራጀና በውጤታማነት እንዲፈጸም ማድረግ ነው።

### 3.2 ዝርዝር ዓላማዎች

1. በጠንካራ አሰራር  የተደራጀ ጠንካራ የፓርቲ መዋቅር መገንባትና ማጎልበት፣
2. በዘመናዊ መረጃና በአሰራር ሥርዓቱ የደረጀ፣ የተጽእኖ አቅሙ የዳበረ ጠንካራ ተቋም መገንባት፣
3. በአመለካከትና በተግባር የተዋሐደ፣ ለውጡን በብቃት መምራት የሚችል አመራር በማረጋገጥ የፓርቲውን የመሪነት ሚና ከፍ ማድረግ፣
4. የሕዝቡን ተሳትፎ፣ ተጠቃሚነትና እርካታ ለማረጋገጥ የሚያስችል አደረጃጀት በመፍጠርና በማጠናከር የመሪነት ሚናቸውን እንዲወጡ ማድረግ፣
5. በፈጠራና በፍጥነት መርህ በመታገዝ ተልዕኮውን በውጤታማነት መፈጠም የሚችል አደረጃጀት ዕውን ማድረግ።

### 3.3 የእቅዱ ግቦች

1. የዝግጅት ምዕራፍ ተግባራት በተሳካ ሁኔታ በመፈጠም ለተግባር ምዕራፍ ምቹ ሁኔታ መፍጣር ተችሏል ።

2. በግልፅ የተልዕኮ ስኬት ላይ የተመሰረተ የምደባ ስርዓት በመዘርጋት እና የምዘናና እውቅና ስርዓት እውን በማድረግ የፓርቲ ተቋማዊ ጥንካሬ ማሣደግ ተችሏል፡፡

3. የፓርቲውን አደረጃጀትና አሰራሮች በማዘመን የፓርቲውን ተቋማዊ ጥንካሬ ተራጋግጧል፣

4. በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብና አሠራር መሰረት ነባሩን አመራርና አባሉን በማጥራት አዳዲስ አባላት ምልመላ በማድረግ የፓርቲውን መሠረት ማስፋት ተችሏል፣

5. በመላ አባላቱ ዘንድ ተቀባይነት ያለው በየደረጃው የውስጥ ምርጫ በማካሔድ የፓርቲውን ዴሞክራሲያዊነት ተረጋግጧል፣

6. ጥራትና ብቃት ያላቸውን ዕጩዎችን ለሚሚያና ለአካባቢያዊ ምርጫ በማዘጋጀት የፓርቲውን ተወዳዳሪነት መራጋገጥ ተችሏል፣

7. የሀገሪቱን ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ፖሊሲዎችን በብቃት ማቀድና መፈፀም የሚችል ተተኪና ኮር አመራር በየደረጃው ማፍራትና ማብቃት ተችሏል፣

8. በከተማ ተቋማት ብቃት ያለው ፖለቲካና የአደረጃጀት ስራ በመስራት እንዲሁም የመልካም አስተዳደር ችግር በመሰረታዊነት በመቀነስ የህዝብ እርካታን ማረጋገጥ ተችሏል ፣

9. ጠንካራ ፓርቲ ለመፍጠር የሚያስችል ውጤታማ የአሰራር ሥርዓት በመዘርጋት በየደረጃው ያለው አስተባባሪና አመራር ኮሚቴ፣ አደረጃጀቶችና የአደረጃጀቶች አመራሮች፣ ቋሚ ግንኙነት ጊዜያቸውን ጠብቀው ግምገማና ውይይት ማካሄዳቸውን ተረጋገጧል፣

**3.4 ግቦችን ለማሳካት የሚከናወኑ ዋና ዋና ተግባራት**

ሁላችንም እንደምንገነዘበዉ የዘርፍ ስራዎች ጠንካራ ፓርቲ ለመገንባት ወሳኝ ነዉ፡፤ በዚህም ሳይወሰን በበጀት አመቱ ለታቀዱ የመንግስትና የፓርቲ ስራወችንም ለማሳለጥ እንዲሁም በየደረጃወ የሚገኙ አደረጃጀቶችን ወደተግባር በማስገባት ከተለማደዉ አካሄድ በመሰረቱ የተለየ ለዉጥ እንድመጣ በዘርፍ የሚከናወኑ ተግባራት ግልፅ ግብ ተቀምጦላቸዉ ሊተገበሩ ይገባል፡፡ በሌላ በኩል ደግሞ የሚታቀዱት ግቦች ለፌደራል ብልፅግና እና ከፅ/ቤቱ መሪ እቀዶች ጋር የተናበቡ መሆናቸዉም ሊረጋጋጥ ይገባል ፡፡ ስለሆነም የዘርፉ 2017 በጀት አመት እቅዶች ከላይ የተገለፁትን ሁሉንም ሁኔታዎች መስረት ያደረጉ ግቦቸን በመቅረፅ እና ተገበራቱንም በመለየት ታቅዶል፡፡ ዋናዋና ግቦችና ተግበራቱም ከዚህ እንደሚከተለዉ ቀርቦል፡፡

**ግብ 1. የዝግጅት ምዕራፍ ተግባራት በተሳካ ሁኔታ በመፈጠም ለተግባር ምዕራፍ ምቹ ሁኔታ መፍጣር ተችሏል**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ዋና ዋና ተግባራት**

- የ2016 በጀት አመት የአደረጃጀት ዘርፍ ሥራዎች እቅድ አፈጻጸም በመገምገም ጥንካሬና ድክመት በመለየትና በማደራጀት ለ2017 እቅድ ግብዓት መጠቀም ተችሏል፣
- የፓርቲ የ10 ዓመት ስትራቴጂና የ2016 በጀት ዓመት የዘርፉ ስራ አፈፃፀም መነሻ በማድረግ የ2017 በጀት ዓመት የዘርፉ እቅድ ማዘጋጀት፣
- በወረዳ 01 ደረጃ ለሚገኙ የአደረጃጀት ዘርፍ የእቅድ ኦሬንቴሽን በመስጠት ከዳበረ በኂላ በተግባር ሥራ እንዲውል መድራግ፣
- ከፓርቲ ቅርጫፍ ጽ/ቤት የተዘጋጀዉን እቅድ መነሻ በማድረግ በወረዳ 01 የአደረጃጀት ዘርፍ እቅድ በማቀድ እና ለሁሉም ፈፃሚ አካላት ኦሬንቴሽን በመስጠት ወደ ተግባር እንድገቡ ማድራግ፣
- በየደረጃው ክፍተት ያለባቸው አደረጃጀቶችን እንደገና መልሶ የማደራጀት፣ የተጓደሉ የአደረጃጀት አመራሮች የማሟላት፣ እንደ አስፈላጊነቱ የችግሩ ስፋት እየታየ በየደረጃው የአመራር መልሶ የማደራጀት ተግባር እንድከነዋን ማድራግ፣
- ሁሉም አመራርና አባላት የግል ዕቅድ እንድያዘጋጅ መድራግ፣
- ለእቅድ ስኬት አስፈላጊው የሆኑ ግብዓቶች መለየትና ለማሟላት የሚያስችል ሁኔታ መፍጠርን የዝግጅት ምዕራፍ ስራን ማጣቃላል፣

**ግብ 2. በግልፅ የተልዕኮ ስኬት ላይ የተመሰረተ የምደባ ስርዓት በመዘርጋት እና የምዘናና እውቅና ስርዓት እውን በማድረግ የፓርቲ ተቋማዊ ጥንካሬ ማሰደግ ተችሏል**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ዋና ዋና ተግባራት**

- የአመራር ምደባ መመሪያ ጸድቆ ስላክ ስራ ላይ እንዲውል በማድረግ በምደባ ላይ ግልጸኝነትን መፍጠር
- የምዘና ማስፈፀሚያ ዕቅድ እራሱን ችሎ እንዲዘጋጅ ማድረግ፣ለሚመለከተው አካል ኦሬንቴሽን በመስጠት አስፈላጊ ቅድመ ዝግጅት ማድረግ፣
- ለምዘና አስፈላጊ የሆኑ ኮሚቴዎችን በየደረጃው በማደራጀትና ሎጂስቲክ የማሟላት ስራ መስራት፣
- የአመራር፣ የአባላትና የመዋቅር ምዘናው በጥራት ወቅቱን ጠብቆ እንዲካሄድ ማድረግ፣
- የምዘናው ውጤት አንድ ደረጃ ከፍ ባለ አመራር እርከን እንዲጸድቅ ማድረግ፣
- የምዘና ውጤት ሁሉም ባሉበት መገምገምና አንዱ ከአንዱ ተሞክሮ የሚለዋወጡበት ሁኔታ መፍጠር፣

- የተጠቃለለ የምዘና ሪፓርት በማዘጋጀት በምዘና የተገኙ ጠንካራና ደካማ ጎኖች በመለየት ለቀጣይ ምዘና በግብዓትነት መጠቀም፣
- የምዘና ውጤቱን ለውስጠ ፓርቲ ጤናማነት እና ውጤታማነት መጠቀም፣
- በዓመቱ የተሻለ አፈጻጸም ላሳዩ አካላት አቅም በፈቀደው መጠን የማበረታቻ እውቅና እንድሰጥ ማድራግ ፣
- የምዘና ውጤት ፕሮፋይል በቅጽ ስድስት በአግብቡ ተሞልቶ በየጽ/ቤቶች እንዲቀመጥና ሲፈለግ ጥቅም ላይ እንዲውል ይደረጋል፣

**ግብ 3. የፓርቲውን አደረጃጀትና አሰራሮች በማዘመን የፓርቲውን ተቋማዊ ጥንካሬ ተራጋግጧል፣**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ዋና ዋናና ዝርዝር ተግባራት**

**ሀ. በየደረጃው ጠንካራ የፓርቲ ተቋማዊ አደረጃጀቶችና አሰራሮች መገንባት ተችሏል፡**

- የፓርቲው አደረጃጀቶች በአደረጃጀትና አሰራር መመሪያ መሰረት የተደራጁ መሆናቸውን የመፈተሽና መልሶ የማደራጀት ተግባራት ማከናወን፣
- በሁሉም አካባቢ አደረጃጀቶች ሙሉ በሙሉ ተደራጅቶ መጠናቀቃቸውን መከታተል፣ መደገፍ፣/ አንድም አባላት ከአደረጃጀት ውጪ እንዳይኖር ይደረጋል
- የውስጠ ፓርቲ ዴሞክራሲያዊነትን በሚያረጋገጥ አግባብ የፓርቲያችን መሰረት የሆኑትን በየአከባቢው የሚገኙ መሰረታዊ ድርጅቶችና ህዋሳት ለማጠናከር እንዲቻል በመላው አባላችን ዘንድ ተዓማንነት ባለው መልኩ የአመራሮች የውስጥ ምርጫ ማካሄድ፣
- አሰራርን ጠብቆ የሚንቀሳቀስና በማንኛውም ጊዜ የፓርቲ ተልዕኮ ተቀብሎ በተግባር ስኬት የሚያስመዘግብ አደረጃጀቶች በየደረጃው መፈጠሩንና መጠናከሩን መከታተል፣ መደገፍ፣ ማብቃት፣
- በየደረጃው ያለው የአመራር ኮሚቴ እንዲሁም አስተባባሪ ኮሚቴዎች ግንባር ቀደምና በአግባቡ ተፅዕኖ የማድረግ አቅም ባላቸው አመራሮች የተደራጀ መሆኑ የመፈተሽ፣ የማረጋገጥና በመደበኛ የግንኙነት ጊዜያቸውን ጠብቆዉ እንድከሄድ ማድራግ
- ከፓርቲ የሚሰጡ ተልዕኮዎች በተደራጀ አግባብ በአደረጃጀቶች እንዲከናወኑ ማድረግ፣
- አደረጃጀቶቻችን በተደራጀ መልኩ ሌብነትና ብልሹ አሰራርን ለመቀነስ የመታገያ መድረክ ሆነው እንዲያገለግሉ መስራት፣

- ደጋፊዎችን በአግባቡ በማደራጀት የፓርቲን ተልዕኮ የመፈጸምን ብቃት ማሳደግ ስራ ይሰራል፣
- በየደረጃ ያሉ የክብር አባላት የምስክር ወረቀት በመስጠት በተገቢው መንገድ በፓርቲ ስራዎች ማሳተፍና ልምዳቸውን መጠቀም ፣
- አደረጃጀቶችን ከተግባርና ሀላፊነታቸው አኳያ በዓመቱ መጨረሻ ላይ መሰረታዊ ድርጅት 90 በመቶ እና ህዋስ 80 በመቶ ግንባር ቀደም እንዲሆኑ በማድረግ አደረጃጀቶቻችንን በሁሉም ተግባር ተፅዕኖ ፈጣሪ እንዲሆኑ ይደረጋል፡፡

**ለ. የፓርቲ አደረጃጀቶች፣ አመራሮች፣ አባላት፣ መረጃ በቴክኖሎጂ የተደገፈና የሚተዳደር እንዲሆን ተደርጓል፣**

- የአመራርና አባላት መረጃ ጥራትን ማዕከል በማድረግ ተጠቃሎ ወደ መረጃ ቋት እንዲገባ ይደረጋል፣ እንዲሁም የአመራር ሲቪና ፎቶ፣ የአባላትን ፎቶ በመረጃ ቋት ተጠናቶ ይገባል፡ ፡ የመረጃ ቋት ሶፍትዌርን የማዘመን ተግባራት ስራ ይሰራል፡፡
- የአመራር፣ የአባላትና የአደረጃጀቶች መረጃ ቋት አጠቃቀም ላይ ለሚመለከተው አካል ግንዛቤ የማስጨበጥ ስራዎችን መስራት፣
- የመረጃ ቋት ላይ በቂ እውቀትና ግንዛቤ ያላቸው ባለሞያዎች እንዲሟሉ ማድራግ፣
- የፓርቲ አደረጃጀቶች፣ አመራሮች፣ አባላት፣ መረጃ በኢንፎርሜሽን ኮሙዩኒኬሽን ቴክኖሎጂ የተደገፈ፣ በሚገባ የተያዘና የሚተዳደር እንዲሆን ማድረግ፣
- መረጃ ቋት ውስጥ የገባ የአመራርና አባል መረጃ በየሦስት ወሩ የማጥራት ስራ መስራት፣
- በተለያዩ አካላት ለሚቀርቡ የአባላት፣ አመራርና አደረጃጀቶች መረጃ ጥያቄዎች ለማስተናገድ የውስጥ አሰራር እንዲዘጋጅ ይደረጋል፣
- በየደረጃው መረጃዎች ለጥንቃቄ ሲባል በባክአፐ እንዲያዙ ይደረጋል፣
- አዲስ የተመለመሉ አባላት ወደ ሙሉ አባልነት ከተሸጋገሩ በኋላ ወደ መረጃ ቋት እዲገቡ ይደረጋል፣
- ከፓርቲው በተለያዩ ምክንያት የሚሰናበቱ አባላት መረጃን በየፈርጃቸው በማደራጀት በመረጃ ቋት የመሰረዝ ስራ ይሰራል፣
- በመረጃ ቋት ውስጥ የገባውን መረጃ የሚመለከታቸው አካላት መጠቀም የሚችሉበት ሁኔታ መፍጠር፣
- የአባላት እና አመራር ማህደሮች እና የተለያዩ የፓርቲ ሰነዶችን በአግባቡ በማደራጀት እንዲያዙ ማድረግ፣

- መረጃ ቋት ስርዓት የማዘመን፣ የማደራጀትና ደህንነት የማስጠበቅ ስራ ከአጋር አካላት ጋር ተቀራርቦ መስራት፡፡

**ሐ. ለፓርቲ አባላት ዲጂታል መታወቂያ መስጠት ተችሏል**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

- ለመታወቂያ አሰጣጥ ወሳኝ የሆነ የአባላት መረጃና ፎቶ በትክክል ወደ ዳታ ቤዝ እንዲገባ የማድረግ ተግባር በቅደሚያ የማጠናቀቅ ስራ ይሰራል፣
- ለዲጂታል መታወቂያ ዝግጅት አስፈላጊ ማቴሪያል የመለየትና የማዘጋጀት ስራ መስራት፣
- የዲጂታል የመታወቂያ የስርጭት ሂደት በቅደም ተከተል አመራር፣ የመንግስት ሰራተኛ፣ ግንባር ቀደም አባላት እንዲሆን በማድረግ የሚሰራ ይሆናል፣

**ግብ 4. በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብና አሠራር መሰረት ነባሩን አመራርና አባሉን በማጥራት አዳዲስ አባላት ምልመላ በማድረግ የፓርቲውን መሠረት ማስፋት ተችሏል፣**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ዋና ዋና እና ዝርዝር ተግባራት**

**ሀ. አመራርና አባላት የማጥራት ስራ በሁሉም እርከን 95% ተከናውኗል፡**

- የአባላት ጥራት መለኪያዎችና ምዘና ሥርዓት በማዘጋጀት የአባላትን የጥራት ደረጃ መወሰንና ማጥራት፣
- በአመለካከትና በተግባር ብልጽግና ያልሆኑ አባላትን መለየት፣ የስነ-ምግባር ብልሽት የሚታይባቸው አባላትና አመራር የፓርቲውን የአሠራር ሥርዓት መሰረት ባደረገ መልኩ ከፓርቲው እንዲሰናበቱ ማድረግ፣
- በተግባራት አፈፃፀም ሂደት ውስጥ የፓርቲውን የአመለካከትና የተግባር አንድነትን የሚጎዱ ማናቸውም ድርጊቶች ሲፈፀሙ ወዲያውኑ የማጥራት ሥራ ይሰራል፣
- በበጀት ዓመቱ በየወሩ የተግባራትን የአፈፃፀም ግምገማ እንዲከናወን ይደረጋል፣ በግምገማ ሂደቱ ውስጥ የማጥራት ተግባራቱን ትኩረት ተሰጥቶ ይሰራል፣
- የፓርቲውን አባላት ከቁጥር ባሻገር በተጨባጭ መኖራቸውን የአባላት ኦዲት ማድረግ፣
- ከማጥራት የሚገኙ ውጤቶችን መነሻ በማድረግ የአቅም ግንባታ ስራዎች እና የአመለካከት ቀረጻ እንዲሁም ወቅታዊና ችግር ፈቺ የማስተካከያ እርምት ለመውሰድ እንዲያስችል ከሚመለከተው አካል ጋር በትብብር መስራት፣

- ካሉን አባሎቻችን መካከል 70 በመቶ የተሰጣቸውን ተልእኮ በመፈፀም ግንባር ቀደም እንዲሆኑ መስራት፣
- በየጊዜው የማጥራት ተግባራት እንደተከናወነ የተሟላ ሪፖርት እንድላክ ይደራጋል
- በየወቅቱ በማጥራት ሒደቱ እንደ ፓርቲ የመጣውን ለውጥ እየመዘኑ መሄድ፣
- በማጥረት ሒደት የተለዩ ዋና ዋና ጉድለቶችንና መንስኤቸውን መለየት፣ በቀጣይ ፓርቲ ወስጥ እንዳይከሰቱ የሚያስችል ስልት መንደፍ፣
- በማጥረት ሂደት ከፓርቲ የወጡ አመራርና አባለትን ሁኔታ በቅርበት መከታተል፣

**ለ. ጥራትን ማዕከል ያደረገ 159 አባላት መመልመል ተችሏል**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

በ2017 የአደረጃጃት ዘርፍ ዋናው ትኩረት ያሉንን አመራር አባለት ማጥራትና መብቃት መሆኑን በመረዳት ለዚህ የሚመጥን ስራ የሚሰራ ይሆናል፡፡

- የበለሀብት አባለት ቁጥር **ከ 29 ወደ 44** መድራስ፣
- አሁን ያለንን 7862 ጥቅር የአባለት ቁጥር 8021 የጠራ አባል ማድረስ መድራስ፣
- የሙሁራን አባለትን አሁን ከለበት 130 ወደ 185 መድረስ
- ከማጥረት ስራችን ጎን ለጎን በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብና የአባላት ምልመላ ስርዓት መሰረት በመደበኛ ስራቸው ግንባር ቀደም የሆኑና በስነ ምግባራቸው የተመሰገኑ 89 ምሁራን፣ ሴቶችንና ወጣቶችን በጥራት የመመልመል ስራ ይሰራል፡፡
- በመጥራትነ በሌሎች ምክንያት የምቀንሱ አባለትን የምተካ ምልመላ መከሄድ
- የምልመላ ፎርሙ በአግባቡ እንዲሞላ እና በየደረጀዉ ለምገኙ ክፍል የማረጋገጥ ይሆናል፣
- የፓርቲውን ፕሮግራምና መተዳደሪያ ደንብ ላይ ግንዛቤ መፍጠር፣
- የተመለመሉ አባላት ለስድስት ወራት የፓርቲ ተልዕኮ እየሰጡ የበቁትን በህዋስ አቅራቢነት በመሰረታዊ ድርጅት ኮንፈረስ ከማጸደቀ በኋላ ወደ መረጃ ቋት የማስገባት ስራ ይሰራል፣
- ምልመላው በተቀመጠው አግባብ መሆኑን በየወቅቱ ማረጋገጥና መፈተሽ፣ ችግር ካለ በፍጥነት የማረም፣ ስራ በጥብቅ ዲሲፕልን እነዲመራ ይደራጋል፣

**ግብ 5. በመላ አባላቱ ዘንድ ተቀባይነት ያለው በየደረጃው የውስጥ ምርጫ በማካሔድ የፓርቲውን ዴሞክራሲያዊነት ማረጋገጥ ተችሏል፣**

**ግቡን ለማሳካት የሚኖረን ተግባር**

- የውስጠ ፓርቲ ዴሞክራሲያዊነትን የሚያረጋግጥና አባላት በፓርቲው ላይ ያላቸውን እምነት ለማሳድግ የውሥጥ ምርጫ ሥርዓት መዘርጋት
- የማስፈጸሚያ ዕቅድ ማዘጋጀትና በማስፈጸሚያ እቅዱ መሰረት የውስጥ ምርጫ አዘጋጅ ኮሚቴ ማደራጀት፣
- አካታችነትና ተመጣጣኝ ውክልናን እውን ማድረግ አመራር ማጠናከር
- የውስጥ ምርጫ ማካሄድ የውድድር መንፈስ ማጠናከር፡፡

**ግብ 6. ጥራትና ብቃት ያላቸውን ዕጩዎችን ለሚሚያና ለአካባቢያዊ ምርጫ በማዘጋጀት የፓርቲውን ተወዳዳሪነት አድጓል፣**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

- በተቀመጠው የጊዜ ሰሌዳ መሰረት ለሚሚያና አከባቢ ምርጫ በሚዘጋጀው መስፈርት መሰረት ፓርቲያችንን የመወክሉ ጥራትና ብቃት ያለቸው እጩዎችን መመልመል፣ ማስተቸትና የተሟላ ፕሮፋይል ማዘጋጀት፣ ስራ ይሰራል፣
- በእጩ ዝግጅት የሚታዩ የአፈፃፀም ክፍተቶች በመከታተል በወቅቱ እያረሙ መሄድ፣
- ፓርቲውን ወክለው ምርጫን የሚታዘቡ ታዛቢዎች የማዘጋጀትና ኦሬንቴሽን ሰጥቶ ማሰማራት፣
- አደረጃጀቶቻችን በምርጫ ስራዎች ላይ በሙሉ አቅማቸው እንዲሳተፉና በአደረጃጀት እንዲሰሩ ማድረግ፣
- በዕጩ ዝግጅት የሴቶች ቁጥር ማሳደግ፣
- የእጩ ዝግጅት አፈፃፀም ላይ የተገመገመ ሪፖርት ማቅረብ፡፡

**ግብ 7. የሀገሪቱን ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ፖሊሲዎችን በብቃት ማቀድና መፈፀም የሚችል ተተኪና ኮር አመራር በየደረጃው ማፍራትና ማብቃት ተችሏል፣ ግቡን ለማሳካት የሚኖሩን ተግባራት**

- የአመራር መረጃ ቋት የማደራጀት ተግባራት ማከናወን፣
- በአመራር ፑል አያያዝና አጠቃቀም ላይ በየደረጃው ላለው አመራር ግንዛቤ ማሳደግ፣
- በኮር አመራር ምልመላና ማብቃት መመሪያ መሰረት መስፈርቱን የሚያሟሉና በውድድር ብቁ መሆናቸው የተረጋገጡ ኮር አመራሮችን የመለየትና የማብቃት ሥራ መስራት፣

- በዚሁ መሰረት በየደረጃው ላለው አመራር እርከን 79 / ወንድ 40 ሴት 39/ ኮር አመራር ይመለመላል፣
- የኮር አመራር ምልመላ በየደረጃ ባለው ፓርቲ ጽ/ቤት አማካይነት ተመልምሎ አንድ ደረጃ ከፍ ባለው መዋቅር የሚጸድቅ ይሆናል።
- በየደረጃው ላለው አመራር እርከን ወረዳ/ 33 ውስጥ 40% ሴት ተተኪ አመራር እንዲመለመል ይደረጋል፣
- የአመራር ሙሉ ፕሮፋይል በተዘጋጀው ዳታ ቤዝ በኦን ላይን እንዲመዘገቡ በማድረግ መረጃውን ማደራጀት፣
- የተተኪና ኮር አመራር ልየታ ወጣቶችንና ሴቶችን ማዕከል እንዲያደረግ የተለየ ትኩረት ተሰጥቶ ይሰራል፣

**ግብ 8. በከተማ ተቋማት የፖለቲካ ስራዎችን በተሳካ ሁኔታ መፈፀም ተችሏል።**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

- አደረጃጀቶች መፍጠር፣ማጠናከር፣የደከሙትን መልሶ ማደራጀት፣
- ነባሩን አመራርና አባላትን በየወቅቱ በማጥራት የአባላትን ጥራት ማስጠበቅ፣
- የአመራር ምዘና፣ምደባ እና ጥሩ አፈጻጸም ያላቸው እውቅና እንዲያገኙ መስራት፣
- ተተኪና ኮር አመራሮችን ለይቶ ስምሪት በመስጠተ ማብቃት፣
- የአባላትና አደረጃጀቶች መረጃ ወደ ዳታ ቤዝ እንዲገባ ማድረግ፣
- የመሰረታዊ ድርጅት ኮንፍረንስ እና ህዋስ ውይይት ወቅቱን ጠብቆ በበቂ ዝግጅት እንድከሄድ ማድራግ፣
- ህዋሳት በመልካም አስተዳደር፣ ሌብነትና ብልሹ አሰራር በወቅታዊ ጉዳዮች ላይ ሳይቆራረጥ እንዲወያዩ ድጋፍ ይደረጋል

**ግብ. 9. ጠንካራ ፓርቲ ለመፍጠር የሚያስችል ውጤታማ የአሰራር ሥርዓት በመዘርጋት በየደረጃው ያለው አስተባባሪና አመራር ኮሚቴ፣ አደረጃጀቶችና የአደረጃጀቶች አመራሮች፣ ቋሚ ግንኙነት ጊዜያቸውን ጠብቀው ግምገማና ውይይት ማካሄዳቸውን ተረጋገጧል፣**

**ግቡን ለማሳካት የሚከናወኑ ተግባራት**

- የፓርቲ መተዳደሪያ ደንብ፣ መመሪያዎችና አሰራሮች ለሁሉም መዋቅር መድረሳቸውንና ስራ ላይ መዋላቸውን የማረጋገጥ ስራ ይሰራል፤
- በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብ፣ መመሪያዎችና አሰራሮች ላይ ለሁሉም የፓርቲ አመራርና አባላት በቂ ግንዛቤ የማስጨበጫ ሥልጠና አቅም ባላቸው አመራሮች እንዲሰጥ ማድረግ፣
- አደረጃጀቶች ለፓርቲው አቅም በሚሆን አግባብ በተከታታይ ቋሚ ግንኙነት ጊዜያቸውን ጠብቀው ውይይት ማድረጋቸውን መከታተል፣ መደገፍ፣ ማረም፣
- በየደረጃው ያለው አስተባባሪና አመራር ኮሚቴ በተቀመጠው የግንኙነት አግባብ እየተገናኙ ተግባሮቻቸውን በመምራት ሚናቸውን እንዲወጡ ማድረግ፣
- የመሰረታዊ ድርጅት፣ የህዋስና የተለያዩ የአደረጃጀት ንዑሳን ኮሚቴዎች አመራሮች ሥራቸውን በተቀመጠላቸው ጊዜ ሰሌዳ እየተገናኙ እንዲገመግሙ፣ የቀጣይ የስራ አቅጣጫ እያስቀመጡ እንዲሄዱ፣ ድክመት ባለበት የእርምት እርምጃ እየወሰዱ መሆኑን ከትትል ማድረግና ተከታታይ ግብረመልስ የመሰጠት ስራ ይሰራል፣
- የአመራር ምደባዎችና ሹመቶች በፓርቲ መመሪያና አሰራር መሰረት ከአመራር ፑል በመውሰድ ስምሪት እንዲሰጥ ይደረጋል፣ ከዚህ ውጭ ያሉ የተለምዶ አከሄዶች እና የአሰራር ክፍተት መፈጠሩ ሲረጋገጥ ወዲያው እንዲታረም ይደረጋል፣
- ፓርቲያችን በየጊዜው የሚያወጣቸው መመሪያዎችና የስልጠና ሰነዶች በሥርዓት ተደራጅተው መያዝና በየጊዜው የሥራ መመሪያ እንዲሆኑ ክትትልና ድጋፍ ማድረግ፣
- በየደረጃው ያሉ አደረጃጀቶችን ለማጠናከር ለአቅም ግንባታና ስልጠና ተግባራት የሚዘጋጁ አመራርና አባላትን በግልፅ መስፈርት መለየት፣ ምልመላውን ማከናወን፤
- የክ/ከተሞች ብልጽግና ፓርቲ ጽ/ቤቶች መካከል የተቀራረበና ወጥ የሆነ አሰራርና አደረጃጀት እንዲሁም ውጤታማ የተግባር አፈጻጸም እንዲኖር የሚያስችል እገዛና ቅርበት ያለው ድጋፈ ማድረግ፣
- የፓርቲው ውስጠ ዴሞክራሲን የሚረጋግጥ ግምገመና ምዘና በተቀመተው አቅጣጫ መስረት እየተከናወነ መሆኑን በመከታተልና መደገፍ፣ ክፍተት ካለ ማስተካካል፣
- የፓርቲውን አሰራርና ደንብ የሚጥሱ አመራር እና አባላት አካላት ላይ በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብና የአባላት ስነ-ምግባር መመሪያ መሰረት እንዲሁም የፓርቲውን ውስጣዊ

ተቋማዊ አሰራር በሚያጠናክር፤ ሀላፊነት የተሞላበትና ግልፀኝነትን ያለው የእርምት እርምጃ እየተወሰደ መሆኑን ማረጋገጥ፣

- የስራ ሪፖርት ቅብብሎሽ በአደረጃጀትና አሰራር መመሪያው በተቀመጠው የግንኙነት አግባብ መሰረት ወቅቱንና ጥራቱን የጠበቀ መሆኑን መከታተል፣ከታች ከህዋስ ጀምሮ ተቋማዊ አሠራሮች በመጠበቅ ውጤታማነትና ችግር ፈቺ የሆኑ ክትትልና ድጋፎችን ማድረግ፣

## 3. ክፍል ሦስት

### 4.1 የአፈጻጸም አቅጣጫና ስልቶች፤ድጋፍና ክትትል፤ ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮች እና መፍትሄዎቻቸው

### 4.2 የምንከተላቸው አፈፃፀም አቅጣጫዎች

የእቅዱ ማስፈፀሚያ አቅጣጫዎች በአደረጃጀት ዘርፍ የተቀመጡ መሪ እቅዲ የተቀመጡት ፣እንዲሁም የጉባኤ አቅጣጫዎች የዚህ እቅድ ማስፈፀሚያ ስልቶች ናቸዉ፡፡ ተግባበሮቻችን ስኬት በጥብቅ የፓርቲ ዲሲፕሊን ላይ የተመሰረተ የክትትልና ድጋፍ ስርዓት መዘርጋት በጣም አስፈላጊ ነው፡፡ የበጀት ዓመቱ እንደ ፓርቲ ጠንካራና ጥራት ያለው ተቋማዊ አደረጃጀት የምፈጥርበት እና በአደረጃጀቶቻችን ግንባር ቀደም መሪነት ለሁለንተናዊ ብልጽግና መሠረት የምጥልበት ዓመት ነው፡፡ ከዚህም በተጨማሪ የጀመርናቸውን ትላልቅ ተግባራት የምናስቀጥልበት፣ ጉድለቶችን የምናርምበት ወቅት ነው፡ ፡ በተለይም የህዝቡን ሠላምና ደህንነት የምናረጋግጥበት፣ ሌብነትና ብልሹ አሰራሮችን በህዝብ ተሳትፎና በፓርቲያችን አባላት ሁለንተናዊ ንቅቀናቄ የምንቀንስበት፣ የተሳሳቱ ትርክቶችን በማረም ሃገራዊ አስተሳሰብና የወል እውነቶች በፓርቲ ውስጥም ሆና በህዝብ ዘንድ እንድጎለብቱ የምንሰራበት፤እንዲሁም ምርጫ ያልተካሄደባቸው አካባቢዎችና የአካባቢ ምርጫ የሚካሄድበት በመሆኑ የተለየ ርብርብ የሚጠይቅ ወሳኝ ጊዜ ነው፡፡ ስለሆነም ሁሉም ተግባሮቻችን በተደራጀ ሁኔታ እንዲፈፀሙ እንደየባህሪያቸው የማስፈፀሚያ ስልት ተነድፎላቸው ተግባራዊ ይደረጋሉ፡፡

- በበጀት ዓመቱ በአደረጃጀት ዘርፍ የተጣለውን ግብ ማሳካት እንዲቻል ሁሉም ተግባሮቻችን የሚለካ፣ የሚቆጠርና የሚጨበጥ ውጤት እንዲያመጡ በትጋት የሚሰራ ይሆናል፡፡በተላይም የፓርቲያችንን ውስጣዊ አንድነት ለማረጋገጥ የሚያግዙ ተግባራት ላይ በማተኮር አመራርና አባላትን ማጥራት፣ በተልዕኮ ማንቀሳቀስ፣ ውጤትን ማዕከል ያደረገ ምዘና ማከሔድ፣በሁሉም እርከን ተፅዕኖ የመፈጠር አቅሙ ያደገ አደረጃጀት መፈጠር ላይ ርብርብ ይደረጋል፡፡ ከዚህ በተጨማሪ የአባላት መረጃ ሙሉ በሙሉ ወደ ዳታ ቤዝ ማስገባት፣

የአባላት መታወቂያ ስርጭት ማከናወን፣ ምልመላን በጥራት ማካሄድና ባለፈው ዓመት በአደረጃጀት መከናወን እየተገባቸው ሳይከናወኑ የቀሩ ተግባራትን ጭምር በዕቅዱ በማካተት የሚሰራ ይሆናል፡፡

- ከላይ ለተዘረዘሩት ተግባራት ስኬት በዘርፉ ያሉ አመራሮችና ፈጻሚዎች በተቀናጀና በተናበበ መንገድ መስራት ይጠበቅባቸዋል፡፡ከዘርፉ ተግባር አፈፃፀም አኳያ ትኩረት ሊሰጠው የሚገባው ጉዳይ በየምዕራፎቹ መፈፀም ያለባቸው ተግባሮች በሙሉ ሳይንጠባጠቡና ወደሌላኛው ምዕራፍ ሳይሸጋገሩ መፈፀማቸውን በጥብቅ ዲሲፕሊን መከታተልና ችግር ሲያጋጥም ቶሎ ማስተካከል ይኖርብናል፡፡
- ሦስቱንም የድጋፍና ክትትል ሥራዎች ተመጋጋቢ በሆነ ሁኔታ መጠቀም፣ በጠራ የመረጃ አያያዝ የተደገፈና ውስጠ ፓርቲ ዲሞክራሲን ባረጋገጠ ትግል መፈጸሙን ማረጋገጥ ይገባል፡ ፡
- በአደረጃጀት ዘርፍ የተዘጋጀ የ2017 ዓ.ም ዕቅድ እስከ ታች (ህዋስ) ድረስ በለው አደረጃጀታችን የሚናበብ፣ የተቀጠረ፣ በውጤት መለካት የሚችል እና የተቀመጠውን አጠቃላይ ግብ ማሳካት የሚችል መሆኑን ማረጋገጥ ይጠይቃል፡፡ ለእያንዳንዱ ግብም የሚያስፈልግ በጀት፣ ዝርዝር ተግባራት፣ ፈጻሚ አከልና የሚፈፀምበት ጊዜን የያዘ የድርጊት መርሃ ግብር ሊቀመጥለት ይገባል፡፡ ተግባራት ሲቀመጡ ፈጻሚዎችን የሚያነቃቁና የሚከታተለውን አመራርም ተቆጥሮ የሚሰጣቸውና የሚረከባቸው መሆን አለባቸው፡፡
- የአባላት ምልመላችን ጥራት ማዕከል ያደረገና ለፖርቲው እሴት የሚጨመሩ ምሁራንን፣ ሴቶች፣ ወጣቶችን በልዩ ትኩረት መመልመል ያስፈልጋል፡፡
- ከሌሎች ዘርፎች ጋር በቅንጅት የሚሰሩ የፓርቲ ተግባራትን ማከናወን

**በ2017 ዓ/ም አንድም**

- በዕቅድ የማይመራ፣
- በአግባቡ ያልተደራጀ፣
- በቋሚነት የማይወያይ፣
- በፓርቲው እሳቤ የማይመራ፣
- የፓርቲውን አሰራር የማይከተል፣
- በተግባር አፈጻጸም የማይመዘን **የብልፅግና ፓርቲ አደረጃጀት፣ አመራርና አባል አይኖረንም**

- የዕለት ተዕለት ሥራዎቻችን በታቀደው መሠረት አጠናክረን መቀጠልና ውጤት የምናስመዘግብበት ዓመት መሆን አለበት፡፡ አመራርና አባላት የፖርቲውን ፕሮግራምና መተዳደርያ ደንብ፣ እሳቤዎችንና እሴቶችን በአግባቡ የተገነዘቡና ራዕይ የሚጋሩ እንዲሆኑ ተከታታይ የዕለት ተዕለት ግንባታ ሥራ መስራት ይኖርበታል፡፡
- ለማረምና ለመገንባት የሚያስችሉ በቅቶ ማብቃት ስትራቴጅን መተግበሪያ ዋነኛ መድረኮች እንዲሆኑ ማድረግ፣ በፖርቲው አባላት ዘንድ መሰረጽ የሚገባቸውን አስተሳሰቦች በተለያየ መልኩ በድግግሞሽ አጀንዳ እንዲሆኑና እንዲሰርጹ ማድረግ የትኩረት አቅጣጫ ነው፡፡
- የአባላት ምልመላ ሥራዎችን ከብዛት ይልቅ ጥራት ላይ ያተኮረ እንዲሆን በማድረግ ለፖርቲው እሴት የሚጨመሩ ሴቶች፣ ወጣቶችንና ምሁራንን ልዩ ትኩረት መመልመል ያስፈልጋል፡፡

### 4.4 ሪፖርትና ግብረመልስ

- በየወሩ ከ 21-23 ድረስ ሪፖርት በፁሑፍ ለዘርፉ መላክ አለበት፡፡
- እንደየሁኔታውና ወቅታዊ ስራን በተመለከተ የሚኖረውን ወቅታዊ ግንኙነትና የመረጃ ፍሰት እንደተጠበቀ ሆኖ ዘርፉ በመደበኛነት በየ15 ቀናት አጭር የቃል ሪፖርት፣ በየወሩ አጭር የፅሑፍ ሪፖርት እና በየ3 ወሩ የተገመገመ የፅሁፍ ሪፖርት ከክፍለ ከተማ አደረጃጀት ዘርፍ በመቀበል ግብረ መልስ ይሰጣል፡
- የማስተባበሪያ ቢሮዎች እና የክፍለ ከተማ የድረጅት ዘርፍ በየአስራ አምስት ቀናት ተግባራትን በጋራ ይገመገማሉ፣ለሚቀጥለው አስራ አምስት ቀናት ተግባራት አቅጣጫ ያስቀምጣሉ፣
- ዘርፉ ከዳይሬክቶሮች ጋር በየሳምንቱ ተግባራትን ይገመግማል፣የቀጣይ አቅጣጫ ያስቀምጣል፣
- የዘርፉ ኃላፍና ምክትል ኃላፍ ከክፍለ ከተሞች ማስተባበሪያዎች ጋር በተመሳሳይ በየ15 ቀኑ ስረዎችን እየገመገሙ ስራዎች ይመራሉ

### 4.5 የመደበኛ ግምገማ መድረክ

- የድርጅት ዘርፍ ከክፍለ ከተማ እና የወረዳ አደረጃጀት ዘርፎች ጋር በስድስት ወር በአካል በመገናኘት ተግባራትን በጋራ ይገመግማሉ፡፡

- አደረጃጀት ዘርፍ ኃላፊው በየሶስት ወሩ ከዘርፉ አመራሮች ጋር ተግባራትን በመገምገም ጥንካሬና ድክመት በመለየት ጥንካሬዎች በማጎልበት ድክመቶች እንዲታረሙ ይደረጋል፡፡

## 4.6 ሱፐርቪዥንና ኢንስፔክሽን

ከፓርቲዉ ጽ/ቤት ጋር በመነጋገር አደረጃጀቶች ያሉበት ሁኔታ በዓመት አራት ጊዜ ሱፐርቪዥን በማካሄድ መልካም ልምዶች ተለይተው እንዲቀመሩና እንዲሰፉ ማድረግ የሚያስችል ክትትልና ድጋፍ በማድረግ ወቅታዊና ችግር ፈቺ ግብረ-መልስ መስጠትና የታዩ ምርጥ ልምዶች ቀምሮ ማስፋት፣ ክፍተቶችን ለይቶ ለመፍታት ድጋፍ በሚመለከታቸው አመራሮች እንዲሰጥ የማድረግ ስራ ይሰራል፡፡

## 4.7 ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮችና የመፍትሔ አቅጣጫዎች

### 4.7.1 ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮች

- የአባላት መረጃ አያያዝና የመረጃ ቋት አጠቃቀም ጉድለትና የጥራት ችግር አለመቀረፍ፣
- የመዋቅራችን የሥራ የተነሳሽነትና ዝግጁነት ችግር መኖር፣
- በአመራር ሥርዓታችን የአስተሳሰብና የተግባር አንድነት አለመጠናከር፣
- ለዘርፉ አዲስ የሆኑ የዘርፍ አመራሮች ያሉ ከመሆኑ ጋር ተያይዞ የዘርፉን ስራዎች በተሟላ ዕውቀት የመምራት ችግር፤
- በሱፐርቪዥን ወቅት በድክመት የተለዩ ግኝቶችን ፈጥኖ የማስተካከል ውስንነት
- የዘርፉን ስራዎችና የሚሰጡ ተልዕኮዎችን ከመደበኛ ስራዎች ጋር አቀናጅቶ መምራት ላይ ያለ ውስንነት

### 4.7.2 ሚወሰዱ የመፍትሄ ሀሳቦች

- መደበኛ የዘርፍ ስራዎችንና ሌሎች ስራዎችን አቀናጅቶ መስራት ፤
- የአባላት መረጃ በጥራት አሟልቶ መያዝ የእያንዳንዱን አባል መረጃ በዳታ ቤዝ ውስጥ ማስገባትና አአጠቃቀሙን ማዘመን፣
- በየደረጃው ካሉት ኃላፊዎች ጋር ውይይት በማድርግ በድክመት የተለዩ ግኝቶችን ፈጥኖ እንዲስተካከሉ ማድራግ
- የአመራር ሥርዓታችን የአስተሳሰብና የተግባር አንድነት ማጠናከር

- በየምዕራፉ አመራንና ፈጻሚ አካላትን የሚመጥን በግምገማዊ ስልጠና በመስጠት የማብቃት ወዘተ... ስራዎች በመስራት ችግሮችን መፍታት፣

## 5. የአደረጃጀት ዘርፍ 2017 ግቦች፣ ዋና ዋና ተግባራትና ቁልፍ የአፈጻጸም አመላካቾች

| ተቁ | ስትራቴጂክ ግቦች፣ ዋና ዋና ተግባራ | 2017 ዕቅድ | የዓመት ዒላማዎች | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | | | ሐም | ነሐሴ | መስከ | ጥቅመ | ህዳር | ታህሳ | ጥር | የካቲ | መጋ | ሚያ | ግን | ሰኔ |
| 1 | በግልፅ የተልዕኮ ስኬት ላይ የተመሰረተ አደረጃጀትና አሰራርን በማዘመንና ተግባራዊ በማድረግ የፓርቲውን ተቋማዊ ጥንካሬ ማረጋገጥ፣ (ክብደት 20) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.1 | በግልፅ የተልዕኮ ስኬት ላይ የተመሰረተ የምደባ ስርዓት በመዘርጋት እና የምዘናና እውቅና ስርዓት እውን በማድረግ የፓርቲ ተቋማዊ ጥንካሬ ማሳደግ( ክብደት 3) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.1.1 | ብቃት ያለው የአመራር ምደባ | በቁ 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 | 33 |
| 1.1.2 | የአመራር ምዘና | 100% | | | | | | | 100% | | | | | 100% |
| 1.1.3 | የአባል የምዘና | 100% | | | | | | | 100% | | | | | 100% |
| 1.1.4 | የመሠረታዊ ድርጅት ምዘና | 100% | | | | | | | 100% | | | | | 100% |
| 1.1.5 | የህዋስ ምዘና | 100% | | | | | | | 100% | | | | | 100% |
| 1.16 | የተሻለ አፈፃፀም ላላቸው አካላት እውቅና መስጠት | በቁጥር 1 | | | | | | | | | | | | 1 |
| 1.2 | የፓርቲውን አደረጃጀትና አሰራሮች በማዘመን የፓርቲውን ተቋማዊ ጥንካሬ ማሳደግ(ክብደት 6.75) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.1 | ጠንካራ የፓርቲ ተቋማዊ አደረጃጀት መፍጠርና መገንባት(ክብደት 2.) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.1.1 | መሰረታዊ ድርጅቶች አደረጃጀት ማጠናከር | 100% | | | 95% | | | 97% | | | 98% | | | 100% |
| 1.2.1.2 | የህዋስ አደረጃጀት ማጠናከር | 100% | | | 96% | | | 98% | | | 99% | | | 100% |
| 1.2.2 | በየደረጃው ያለው አስተባባሪና አመራር ኮሚቴ፣ የአደረጃጀቶች አመራሮች፣ መሰረታዊ ድርጅት ኮንፈረንስ፣ የሕዋስ ውይይት በተከታታይ ቋሚ ግንኙነት ጊዜያቸውን ጠብቀው ግምገማና ውይይት ማካሄዳቸውን ማረጋገጥ(ክብደት1.25) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.3.1 | የአስተባባሪ ኮሚቴ የግንኙነትና የግምገማ ስርዓትን ማጠናከር | በቁ 12 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 |
| 1.2.3.2 | አመራር ኮሚቴ ውይይትና ግምገማ | በቁ 24 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 | 2 |
| 1.2.3.3 | የአደረጃጀት አመራሮች የግንኙነትና የግምገማ ስርዓት ማጠናከር | በቁ 12 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 |
| 1.2.3.4 | የመሰረታዊ ድርጅት ኮንፈረንስ | በቁ 4 | | | 1 | | | 1 | | | 1 | | | 1 |
| 1.2.3.5 | የሕዋስ ውይይት ማካሄድ | በቁ 12 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 | 1 |
| 1.2.3.6 | ለአቅም ግንባታና ስልጠና ተግባራት የሚዘጋጁ አመራር በግልፅ መስፈርት መለየት | በቁ 33 | | 33 | | | | 33 | | | 33 | | | 33 |
| 1.2.4 | የፓርቲ አደረጃጀቶች፣ አመራሮች፣ አባላት፣ መረጃ በቴክኖሎጂ የተደገፈ፣ የሚተዳደር እንዲሆን ማድረግ(ክብደት 3.25) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.2.4.1 | ጥራትና ብቃት ያለው የአመራርና አባላት መረጃን ወደ ዳታ ቤዝ ማስገባት | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% |
| 1.2.4.2 | መረጃን በየወቅቱ በማጥራት የመረጃ ተአማንነት ማረጋገጥ | በቁ 2 ጊዜ | | | | | | 1 | | | | | | 1 |

| | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| 1.2.4.3 | የአባላት መታወቂያ ዲጂታል የተደረገዉን መሰራጫት | በቁ 2 | | | | | | | | | | | | |
| 1.3 | በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብና አሠራር መሰረት ነባሩን አመራርና አባሉን በማጥራት አዳዲስ አባላት ምልመላ በማድረግ የፓርቲውን መሠረት ማስፋት(ክብደት 4) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.3.1 | አባላት ማጥራት | 100% | | | 95% | | | 97% | | | 99% | | | 100% |
| 1.3.2 | አመራርን ማጥራት | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% |
| 1.3.3 | ምሁራን፣ ሴቶችንና ወጣቶችን/ ላይ ያተከረ ምልመላ | 50 | | | 50 | | | 50 | | | 50 | | | 50 |
| 1.3.4 | የተመለመሉትን ማብቃት/ማወያየት/ | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100 % | | | 100% |
| 1.4 | በመላ አባላቱ ዘንድ ተቀባይነት ያለው በየደረጃው የውስጥ ምርጫ በማካሔድ የፓርቲውን ዴሞክራሲያዊነትና አመራር ማረጋገጥ (ክብደት 2) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.4.1 | የውስጠ ፓርቲ ምርጫ በማካሄድ የፓርቲን ጥንካሬ ማጎልበ | 70% | | | | | | 65% | | | 68% | | | 70% |
| 1.4.2 | አካታችነትና ተመጣጣኝ ውክልናን እውን ማድረግ አመራር ማጠናከር | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% | | | 100% |
| 1.5 | ጥራትና ብቃት ያላቸውን ዕጩ ለሀገራዊና ክልላዊ ምርጫ በማዘጋጀት የፓርቲውን ተወዳዳሪነት ማሳደግ (ክብደት 0.5) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.5.1 | ዕጩ በጥራት ማዘጋጀትና ማስተቸት | 100% | | | | | | | | | | | | 100% |
| 1.5.2 | በዕጩ ዝግጅት የሴቶች ተሳትፎ 50% ማሳድግ | 100% | | | | | | | | | | | | 100% |
| 1.6 | የሀገሪቱን ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ማህበራዊ ፖሊሲዎችን በብቃት ማቀድና መፈፀም የሚችል አመራር በየደረጃው ማፍራትና ማብቃት(ክብደት 1) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.6.1 | በኮር አመራር ምልመላና ማብቃት መመሪያ መሰረት መስፈርቱን የሚያሟሉና በውድድር ብቁ መሆናቸው የተረጋገጡ ተተኪና ኮር አመራሮችን የመለየትና የማብቃት ሥራ መስራት ( ክብደት 1) | | | | | | | | | | | | | |
| 1.6.1.1 | በመስፈርቱ መሰረት ተተኪ አመራር መለየትና ማጠናከር | በቁ | | | | 167 | 167 | 167 | 167 | 167 | 167 | 167 | 167 | |
| 1.6.1.2 | ኮር አመራር መለየትና ማጠናከር | በቁ 42 | | | | 42 | | | 42 | | | 42 | | 42 |

| ሠንጠረዥ1 የግንባር ቀደም፣ ተተኪና ኮር አመራር ምልመላ ዕቅድ | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ተቁ | ክፍል ከተማ | ግንባር ቀደም አባላት | | | ተተኪ አመራር | | | ኮር አመራር | | |
| | | ወ | ሴ | ደምር | ወ | ሴ | ድምር | ወ | ሴ | ድምር |
| 11 | ቦሌ ወረዳ 01 | 1283 | 1436 | 2719 | 99 | 110 | 209 | 12 | 7 | 19 |

| ሠንጠረዥ 2 የአባላት ምልመላ ዕቅድ 371 | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ተቁ | ክፍል ከተማ | ከተፅዕኖ ፈጣር ወጣቶች | | | ከምሁራን | | | ከበለሃብቶች | | | ከሌሎች | | |
| | | ወ | ሴ | ደምር | ወ | ሴ | ድምር | ወ | ሴ | ድምር | ወ | ሴ | ድምር |
| 1 | ቦሌ ወረዳ 01 | 71 | 64 | 135 | 35 | 30 | 65 | 25 | 15 | 40 | 53 | 78 | 131 |

ማጠቃለያ

እንደ ዘርፍ የፓርቲዉን መሪ እቅድ መነሻ በማድረግ  የዘርፉን  መሬ እቅድ ዕቅደን ወደ ተግባር የገባን መሆኑ ይታወቃል በርካታ ዉጤቶችም መተዋል ይሁን እንጂ በበጀት ዐመቱ መከናወን ያለባቸዉን ተግባራት ከክ/ከተማ ዘርፍ ጋር በመናበብ የተከለሰ እቅድ ዕቅደን ወደ ተግባር መግባት ዕስፈላጊ በመሆኑ ሁሉም ከላይ በዝርዝር የታቀዱ እቅዶችን ዉጤታማ ለማድረግ የፓርቲያችን መዋቅር የወረዳዉን ንዋሪ በማስተባበር ከምንጊዜዉም በላይ በመተባበር እና በቅንጅት መስራት ያስፈላጋል ::